# ክፍል አንድ

ይህ መጽሐፍ - **መድሎተ ጽድቅ - ቅጽ ፪** - የመጀመሪያውን ክፍል እና በውስጡ የተካተቱትን 5 ምዕራፎች የያዘ ሲሆን፥ እያንዳንዳቸው ምዕራፎች የተሐድሶ ፕሮቴስታንቶችን "ብቻ" የሚሏቸውን አስተምህሮዎች የሚዳስሱ ናቸው፡፡ እነዚህም፥

ምዕራፍ 1 — "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ"

ምዕራፍ 2 — "ጸጋ ብቻ"

ምዕራፍ 3 — "እምነት ብቻ"

ምዕራፍ 4 — ክርስቶስ ብቻ"

ምዕራፍ 5 — "ክብር ለእግዚአብሔር ብቻ" ናቸው፡፡

እነዚህ ጉዳዮች የተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች መሠረታዊ እምነቶቻቸውና አስተምህሮዎቻቸው እንደ መሆናቸው እያንዳንዳቸውን በመጽሐፍ ቅዱስ መሠረት መመርመርና መመዘን ተገቢ ነው፡፡ ስለዚህም በዚህ መጽሐፍ ውስጥ እነዚህን **"ብቻ"**ዎች እያንዳንዳቸውን በየምዕራፉ በጥልቀት እንመረምራቸዋለን፡፡

በመጀመሪያው ምዕራፍ ላይ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ - ሶላ ስክሪፕቱራ" የሚለውን በመመርመር እንጀምራለን፡፡ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ በእውነት መጽሐፍ ቅዱሳዊ መሠረት አለውን? ይህን ሐሳብ መጽሐፍ ቅዱስ ይደግፈዋልን? በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚል ቃል ወይም ጥቅስ ይገኛልን? መጽሐፍ ቅዱስን የሚያከብርና የሚያስከብር አስተምህሮስ ነውን? ይህ አስተምህሮ በሐዋርያት እና ከእነርሱ ቀጥሎ በተነሡ የቤተ ክርስቲያን አባቶች ዘንድስ የነበረ አስተምህሮ ነውን? እንዴትና መቼ ተጀመረ? ውጤቱስ ምን ሆነ? የሚሉትን ጉዳዮች እያነሣን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን ጉዳይ አብረን እንመርምረው፡፡ ስለዚህ ወደ ምዕራፍ አንድ እንግባ፡፡

# ምዕራፍ አንድ

## "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ - Sola Scriptura"

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ - Sola Scriptura" የሚለው አስተምህሮ ከአምስቱ የፕሮቴስታንቶች "ብቻዎች - Solas" አንደኛው ሲሆን ዋናውና መሠረታዊው አስተምህሯቸው ነው። ይህን የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ ወደ መመርመር ከመግባታችን በፊት ኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ስለ መጽሐፍ ቅዱስ ያላትን አስተምህሮ በአጭሩ መዳሰስ አስፈላጊ በመሆኑ ከዚህ እንጀምራለን።

### 1.1 መጽሐፍ ቅዱስ እና ኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን

ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን እንደ መጽሐፍ ቅዱስ የምታከብረው መጽሐፍ የላትም። ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን "አምላካውያት መጻሕፍት"፣ "እስትንፋሰ እምላካውያት"፣ "አሥራው መጻሕፍት"፣ "ቀኖናውያት መጻሕፍት" በማለት የምትጠራቸው ብቸኛ መጻሕፍት የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ናቸው። በአጠቃላይ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን "ቅዱስ" ብላ ቅድስናውን እውቅና ሰጥታ በእጅጉ አክብራ ትይዘዋለች ትጠቀምበታለች።

የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት "አሥራው መጻሕፍት" ማለትም ሥሮች፣ መሠረቶች ሲባሉ ከመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ባሻገር ያሉና ይዘታቸው ከመጽሐፍ ቅዱስ ተስማሚ የሆኑ መጻሕፍት ደግሞ "አዋልድ መጻሕፍት" ይባላሉ። ይህም ማለት የመጽሐፍ ቅዱስ ልጆች፣ ከመጽሐፍ ቅዱሰ የተወለዱ፣ የተገኙ መጻሕፍት ማለት ነው።

ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን የምታከብርባቸው ብዙ ምክንያቶች ያሉ ሲሆን ዋና ዋናዎቹን እንደሚከተለው በአጭሩ አንሥተን እናልፋለን።

**1) እግዚአብሔር ራሱን እና ፈቃዱን ለሰው ልጆች የገለጠበት መጽሐፍ ስለሆነ**

እግዚአብሔር ለእኛ የገለጠልንን እርሱነቱን እና ቅዱስ ፈቃዱን በዋናነት የምናገኘው በቅዱሳት መጻሕፍት ነው። መጽሐፍ ቅዱስን በአግባቡ ከተረዳነው ስለ እግዚአብሔር ባሕርይ፣ ስለ ሰው ሁኔታ፣ ስለ ዓለሙ አጠቃላይ አፈጣጠርና አኗኗር ዋናውና የመጀመሪያው ምንጭ ነው። እነዚህን እውነታዎች የሚፈልጉ ሁሉ ቅዱሳት መጻሕፍትን ሊመለከቱ ግድ ይላቸዋል።

**2) የእግዚአብሔር እስትንፋስ (ቃል) ስለሆነ**

አንድን መልእክት የሚያነብብ ሰው የሚገናኘው በዚያ መልእክት ላይ ካለው ሐሳብ ጋር ነው። ያ ሐሳብ ደግሞ የላኪው እስትንፋስ ነው። እንደዚሁም ሁሉ መጽሐፍ ቅዱስ የአስጻፊው የእግዚአብሔር ሐሳብና እስትንፋስ ነው። መጽሐፍ ቅዱስ በተደጋጋሚ ሲናገር የምናገኘው "የእግዚአብሔር ቃል በራእይ ወደ አብራም መጣ . . ."፤ (ዘፍ. 15፥1)፤ "የእግዚአብሔር ቃል ወደ ዳዊት ባለ ራእይ ወደ ነቢዩ ወደ ጋድ እንዲህ ሲል መጣ። . . ." (2 ሳሙ. 24፥11)፤ "የእግዚአብሔር ቃል ወደ እኔ እንዲህ ሲል መጣ።" (ኤር. 1፡4)፤ . . . ሲል ነው። ስለዚህም የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት "እስትንፋስ አምላካውያት" ናቸው የምንለው ለዚህ ነው።

**3) በራሱ በእግዚአብሔር ትእዛዝ የተጻፈ መጽሐፍ ስለሆነ**

መጽሐፍ ቅዱስ የተጻፈው በሰዎች ትእዛዝ ሳይሆን ለእኛ የሚጠቅመንን የሚያውቅና የሚያደርግ ቸሩ አምላካችን እግዚአብሔር እርሱ ራሱ ያስጻፈልን መጽሐፍ ነው። "እግዚአብሔርም ሙሴን፡- የአማሌቅን ዝክር ከሰማይ በታች ጨርሼ እደመስሳለሁና ይህን ለመታሰቢያ በመጽሐፍ ጻፈው" ብሎታል። ዘጸ. 17፡4። እንዲሁም "የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፡- የነገርሁህን ቃል ሁሉ በመጽሐፍ ጻፍ።" (ኤር. 30፡2)፤ "ለሚመጣውም ዘመን ለዘላለም እንዲሆን በሰሌዳ ላይ በመጽሐፍም ውስጥ ጻፍላቸው።" (ኢሳ. 30፡8) ፤ "እግዚአብሔር ለሕዝቡ በመጽሐፍ ይነግራቸዋል።" (መዝ. 86፡6) የሚሉት ሁሉ ይህንኑ የሚናገሩ ቃሎች ናቸው።

**4) እግዚአብሔር እርሱ በመረጣቸው ቅዱሳን ሰዎች አማካይነት የእርሱ ጥበቃ ሳይለያቸው ያስጻፈው ልዩ መጽሐፍ ስለሆነ**

እግዚአብሔር የሚጽፉ ሰዎችን መርጦ አስጻፈልን እንጂ የመጽሐፍ ጥቅል ከሰማይ አላወረደም። እግዚአብሔር የተጠቀለለ መጽሐፍ ከሰማይ ወደ ሰው አላወረደም። እግዚአብሔር ሰዎች የእርሱን ፈቃድ ይሠሩ ዘንድ የሚመርጥና ሥራቸውን መሥራት የሚያስችላቸውን ጸጋውን የሚሰጥ የቅርብ አምላክ እንጂ መጽሐፍን መጻፍ የማይችል እስኪሆን ድረስ ሰውን የሚንቅና የሩቅ አምላክ አይደለምና። ሐዋርያው "ይህን በመጀመሪያ እወቁ፤ በመጽሐፍ ያለውን ትንቢት ሁሉ ማንም ለገዛ ራሱ ሊተረጉም አልተፈቀደም፤ ትንቢት ከቶ በሰው ፈቃድ አልመጣምና፣ ዳሩ ግን በእግዚአብሔር ተልከው ቅዱሳን ሰዎች በመንፈስ ቅዱስ ተነድተው ተናገሩ" በማለት ይህን በግልጽ አስረድቷል። 2 ጴጥ.1፡20

**5) በመልካም ልቡና ሆነው የሚያነቡትን ወደ ቅድስና የሚመራ ስለሆነ**

መጽሐፍ ቅዱስ የተጻፈበት ዓላማ አለው። እርሱም በተጻፈበት መንፈስ ሆነው የሚያነቡትንና የሚማሩትን ሰዎች ወደ እግዚአብሔር ማድረስና ወደ ቅድስና

መምራት ነው። የመጽሐፍ ቅዱስ ዋና ዓላማ ለሰዎች የመዳን እውቀትን መስጠት
ነው። "የመዳንን እውቀት ለሕዝቡ ትሰጣለህ" እንዲል። ሉቃ. 1፡77 ሐዋርያው ይህን እንዲህ
ገልጾታል፡-

> ከሕፃንነትህም ጀምረህ ክርስቶስ ኢየሱስን በማመን፣ መዳን የሚገኝበትን ጥበብ ሊሰጡህ የሚችሉትን ቅዱሳን መጻሕፍትን አውቀሃል። የእግዚአብሔር ሰው ፍጹምና ለበጎ ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ፣ የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ ለትምህርትና ለተግሣጽ ልብንም ለማቅናት በጽድቅም ላለው ምክር ደግሞ ይጠቅማል። 2 ጢሞ. 3፡ 15-17

### 6) እውነት ስለሆነ

እንደ መጽሐፍ ቅዱስ ምድራዊ ብቻ ያይደለ ሰማያዊ እውነትን የያዘ መጽሐፍ
በምድራችን ላይ አይገኝም። መጽሐፍ ቅዱስ የያዘው ራሱ እውነት የሆነው ባለቤቱ
ጌታችን "አማን አማን እብለከሙ - እውነት እውነት እላችኋለሁ" እያለ ያስተማረውን እውነት
ነው። መጽሐፍ ቅዱስ የሚናገረው ስለሚያልፈው ስለዚህ ዓለም እውቀት ሳይሆን የዚህ
ዓለም ገገርዎችና ጠቢባን በእውቀታቸው ሊደርሱበት ስለማይቻላቸው መንፈሳዊና
ዘለዓለማዊ እውነት ነው። በመዝሙረ ዳዊት "በምድር ላይ እንደ ተፈተነ ሰባት ጊዜ እንደ
ተጣራ ብር፣ የእግዚአብሔር ቃላት የነጹ ቃላት ናቸው" ተብሎ የተገለጠው ይኸው ነው። መዝ.
11፡6 እንዲሁም ራሱ ጌታችን "ቃልህ እውነት ነው" (ዮሐ. 17፡17) በማለት፣ የተገለጠው
ይኸው እውነትነቱ ነው። ዕብ. 13፡8

ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስ በውስጡ ከነገረ ሃይማኖታዊም ሆነ ከሥነ ምግባራዊና
ከታሪካዊ ስህተቶች ንጹሕ ነው። ሆኖም መጽሐፍ ቅዱስ ከእናት ቋንቋው
ከዕብራይስጥና ከጽርዕ ወደ ሌሎች ቋንቋዎች ሲተረጎም ሐሳቡ ሳይዛነፍና ሳይሸራረፍ
በሚተረጎምበት ቋንቋ እንዲገለጥ ግን የተርጓሚዎቹ ኃላፊነት ጉዳይ አለበት።

### 7) የቅድስት ቤተ ክርስቲያን የአምልኮዋ አካል ስለሆነ

የኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ሥርዐተ አምልኮዋ በቅዱሳት መጻሕፍት
የተመሠረተና እነርሱንም በተግባር የሚገልጥ ነው። እንዲሁም መጽሐፍ ቅዱስ
የኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን የትውፊቷ ዋና አስረጅና ገላጭ ነው። ለአብነትም
በጸሎተ ቅዳሴ ጊዜ ካህኑ ወደ ቤተ መቅደስ በሚገባበት ጊዜ ከዳዊት መዝሙር
የሚከተሉትን መዝሙራት ይጸልያል፡- መዝ. 24ን፣ መዝ. 60ን፣ መዝ. 101ን፣ መዝ. 102ን፣
መዝ. 129ን ፤ መዝ. 130ን።

ጸሎተ ቅዳሴው ከተጀመረ በኋላ ደግሞ በቅዳሴው ጊዜ ከ14ቱ የቅዱስ ጳውሎስ መልእክታት መካከል አንድ ይነበባል። ከ7ቱ መልእክታትም እንደዚሁ አንድ ይነበብና ቀጥሎ ደግሞ የሐዋርያት ሥራ ይነበባል። በመቀጠልም ከዳዊት መዝሙር ተመርጦ ምስባክ ይሰበካል። ከዚህ በኋላ በታላቅ አክብሮት ሆኖ በዜማ "ወንጌል" ተብሎ ከተዜመ በኋላ ቅዱስ ወንጌል ይነበባል። ከተነበበ በኋላም ሲነበብ የቆየውን ያን መጽሐፍ ቅዱስ ስለ ፍቅራችንና ክብራችን "ነአምን በቃለ ወንጌልከ ቅዱስ - በቅዱስ ወንጌልህ እናምናለን" እያልን እንስመዋለን እንሳለመዋለን።

በታላቁ የጌታችን ጾም (በዐቢይ ጾም) ጊዜም መዝሙረ ዳዊት በየቀኑ ሙሉው በማስተዛዘልና በዜማ ይደረሳል። ትንቢተ ኢሳይያስም ሙሉው ይነበባል። ቅዳሜ ለእሑድ ሌሊት ደግሞ ከብሉይ ኪዳን ውስጥ ያለው የእነ ሙሴ ጸሎት፣ የእነ ሐና ጸሎትና የሌሎቹም ነቢያት ጸሎት ሰማያዊ በሆነ ዜማ ሲጸለይ ይታደራል። በዚሁ ሌሊት ከዳዊት መዝሙርም እንዲሁ በልዩ ዜማ ሲዘመር ይታደራል።

በአጠቃላይ መጽሐፍ ቅዱስ - የእግዚአብሔር እስትንፋስ፣ የከበረ፣ የተለየ፣ እውነት የሆነና የቤተ ክርስቲያን የአምልኮዋ አካል የሆነ ልዩና ቅዱስ መጽሐፍ ነው።

## 1.2 ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች እና "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ"

ፕሮቴስታንቶች የእምነታችን መሠረቶች ናቸው ከሚሏቸው "ብቻዎች" አንደኛው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ - ሶላ ስክሪፕቱራ" የሚሉት ነው። ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶችም እንደዚሁ ይህን በተመለከተ "የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ተሐድሶ" በሚለው መጽሐፍ ላይ "የፕሮቴስታንት ተሐድሶ አምስቱ ምሰሶዎች" በሚል ርእስ ከገጽ 230-248 ተጽፏል። የዚህ መጽሐፍ የመጀመሪያው ክፍል - **ክፍል አንድ** - እነዚህን "ብቻዎች" በእያንዳንዳቸው የሚዳስስ ክፍል ነው። በዚህ ምዕራፍ ደግሞ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው "ምሰሷቸው" ምን ያህል ጥንካሬ ያለው ምሰሶ መሆኑን እንመለከታለን። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ - ሶላ ስክሪፕቱራ" የሚለው አስተምህሮ የፕሮቴስታንቶች ይፋዊ አስተምህሮ እና አቋም መሆኑ የታወቀ ስለሆነ ጉዳዩ የሚታየውና የሚዳሰሰው በዚሁ አግባብ መሆኑን በቅድሚያ መግለጽ አስፈላጊ ነው።

"የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ተሐድሶ" የሚለው የተሐድሶዎች መጽሐፍ በገጽ 231 ላይ "ለድነት መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ብሎ ይጀምርና ለዚህ "ምሰሷችን ነው" ላለው ትምህርት ምንጩ ከየት እንደሆነ ማስረጃ ሲጠቅስ እንዲህ ይላል፡-

- "የጥንት የቤተ ክርስቲያን አበው ከፕሮቴስታንት ተሐድሶ በፊት 66ቱን የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ብቸኛነትና ቅዱስነት እንዲህ መስክረዋል።"

ምስክር አድርጎ የጠቀሰው መጽሐፍ ቅዱስን ሳይሆን ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ያሉ "አበውን" ነው። ተሐድሶው ጸሐፊ ይቀጥልና "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ለሚለው ምሰሶው ምስክር ናቸው ያላቸውን አበው እንዲህ ይጠቅሳቸዋል፥-

- "ቅዱሳት መጻሕፍት /66ቱ/ በመንፈስ ቅዱስ የተጣሩና የነጠሩ አንድ መንፈስ ያላቸው ናቸው።" **ቅዱስ ቴዎፍሎስ**
- "ቅዱሳት መጻሕፍት /66ቱ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ/ ከእግዚአብሔር እና የወጡ በመንፈስ ቅዱስ ምሪት ለሰው የተነገሩ የልዑል ቃላት ናቸው።" **ቅዱስ ቀሌምንጦስ**
- "ቅዱሳት መጻሕፍት /66ቱ/ ፍጹማንና የነጠሩ ናቸው፤ ቃላታቸው በመንፈስ ቅዱስ የተቃኙና የተፈተሹ ናቸው።" **ቅዱስ ሄሬኔዎስ**
- "ታላቁ አትናትዮስ ሊቀ ጳጳስ ዘእስክንድርያ ስለ 66 መጽሐፍ ቅዱስ ሲናገር፥- አምላካውያን መጻሕፍት 66ቱ ናቸው። ለሕይወት ይነበቡ ሲል ተናግሯል። የፕሮቴስታንት ተሐድሶ ከላይ በተመለከትናቸው አባቶች እውቅና ባገኘው 66ቱ መጻሕፍት ላይ የተመሠረቱ ናቸው።" (ገጽ 233-34)
- "...እንግዲህ የአዋልድን መጻሕፍት ላለመቀበል የወሰኑ አብያተ ክርስቲያናት ከላይ የተጠቀሱ **የጥንት የእምነት የአበው ትልቅ ውሳኔ በማክበርና** የ66 የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቀኖናዊነት በመረዳት እንደሆነ ይናገራሉ።" (ገጽ 241)

"ጥንታውያን የኦርቶዶክስ አባቶች እነርሱ ተቀብለው ለእኛ ያስተላለፉልን መልእክት ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ባዕድ ቃል እንዳንሰማ ያዝዛል። ለምሳሌ **ዮሐንስ አፈ ወርቅ** "ባዕድ ቃል ወደ ልባችን እንዳይገባ የመለኮትን ቃላት ማድመጥ ይገባናል" ብሏል። (ስምዐ ጽድቅ ብሔራዊ፣ ገጽ 48 ፤ የተቀበረ መክሊት ገጽ 175 ላይ በድጋሚ የተጠቀሰ)

በጣም የሚገርመው ነገር ደግሞ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ይህ ተሐድሶ ፕሮቴስታንት፣ ስለ መጽሐፍ ቅዱስ ምስክር አድርጎ የአንግሊካን (የእንግሊዝ) ፕሮቴስታንቶችን የእምነት መግለጫ መጥቀሱ ነው። እንዲህ ይላል፥-

- "አበው ከዛሬ 500 ዓመት በፊት ስለ መጽሐፍ ቅዱስና ስለ አዋልድ መጻሕፍት ያወጡትን የሃይማኖት መግለጫ ማወቅ ለዛሬ መረዳታችን ትልቅ መሠረት ነው። በ1643 ዓ. ም. በለንደን ኢንግላንድ በዌስትሚኒስትር ጉባኤ የዌስትሚኒስትር የእምነት መግለጫ (Westminister Confession of Faith) አውጥተው ነበር። ይህን የሃይማኖት መግለጫ የኦርቶዶክስ ፕሬስባይቴሪያን ቤተ ክርስቲያን እንደ ሃይማኖት መመሪያዋ ትጠቀማለች። በዚህ የሃይማኖት መግለጫ ስለ መጽሐፍ ቅዱስ በዚያ ዘመን የነበሩ የቤተ ክርስቲያን መሪዎችና ሊቃውንት ሲናገሩ . . ." (ገጽ 239)

ስለ መጽሐፍ ቅዱስ ተሐድሶ ፕሮቴስታንት፤ ጸሐፊ ካነሳቸው ሐሳቦች ላይ መሠረታዊ የሆኑ ተፋልሶዎቻቸውንና ስህተቶቻቸውን በትንሹ ብቻ እንደሚከተለው ዳስሰን ዋናውን ጉዳይ ከታች እንመለከታለን።

1) "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ካልክ፣ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ያሉ ሌሎች ድርሰቶችን ለምን ትጠቅሳለህ? እነዚህ ምስክር ተደርገው የተጠቀሱት (ቅዱስ ቴዎፍሎስ፣ ቅዱስ ቀሌምንጦስ፣ ቅዱስ ሄሬኔዎስ፣ ታላቁ አትናቴዎስ፣ ዮሐንስ አፈ ወርቅ) እንዳቸውም በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያለ ቃል አይደለምና። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሯቸውን ሊያስረዱን የሚገባቸው ከራሱ ከመጽሐፍ ቅዱስ ይህን የሚያስረዳ ምስክር በማምጣት ነበር እንጂ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ ሌላ ምስክር በመጥቀስ ሊሆን አይገባም ነበር። ይህ ራስን በራስ መቃወም ነው። ይህም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ብሎ የተነሣውን ምሰሷቸውን አንድ ስንዝር ሳይራመዱ ራሳቸው ማፍረሳቸውን ያሳይባቸዋል። ስህተት እንደዚህ ነው፣ ሌላ አፍራሽ ሳያስፈልገው ራሱን በራሱ ሲያፈርስ ይገኛል።

2) እነዚህ የጠቀሷቸው አባቶች ስለ ቅዱሳት መጻሕፍት መልካምነትና ጥሩነት ተናገሩ እንጂ አንድም ቦታ ላይ "የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት 66 ናቸው" አላሉም። ስለሆነም "ቅዱሳት መጻሕፍት" ከሚለው ቀጥሎ በቅንፍ ውስጥ **/66ቱ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ/** ብለህ የጨመርከው የራስህን እምነት እነዚህ አባቶች ያሉ ለማስመሰል የጨመርከው የራስህ ሐሳብ እንጂ እነዚያ አባቶች "መጽሐፍ ቅዱስ 66 ነው" አላሉም። ይህ ፍጹም ሐሰት ነው። እነዚህ አባቶች ስለ ቅዱሳት መጻሕፍት ጠቃሚነት ተናገሩ እንጂ ቅዱስ ቴዎፍሎስም፣ ቅዱስ ሄሬኔዎስም፣ ቅዱስ ቀሌምንጦስም፣ ዮሐንስ አፈ ወርቅም እንዳቸውም ቁጥራቸው 66 ነው አላሉም፣ በጭራሽ! ቅዱስ አትናቴዎስ የዘረዘራቸው የመጻሕፍት ዝርዝር ደግሞ 65 እንጂ 66 አይደለም። ስለሆነም "የጥንት የቤተ

ክርስቲያን አበው ከፕሮቴስታንት ተሐድሶ በፊት የ66ቱን የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ብቸኝነትና ቅዱስነት መስክረዋል" ያልከው ፍጹም ውሸት ነው።

ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች ሆይ፣ መጀመሪያ እናንተ ራሳችሁ መጽሐፍ ቅዱስ 66 ስለ መሆኑ ከራሱ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ማስረጃ አምጡልን! ሌላውን መተቸት የሚቻለው መጀመሪያ የራስን አስተምህሮና ሕግ ካከበሩ በኋላ ነዋ! መጽሐፍ ቅዱስ ራሱ "በውስጤ ያሉት መጻሕፍት 66 ብቻ ናቸው፣ ስማቸውም እገሌ እገሌ ነው" ይላልን? እንደዚሁም "በእኔ ውስጥ የሚካተቱት መጻሕፍት ይህን ይህን የሚያሟሉ ናቸው" ይላልን? ታዲያ እንደዚህ የሚል ካልሆነ መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሌለ ነገር ለምን ትቀበላላችሁ? እናንተ ራሳችሁ የማታምኑበትን ነገርስ ሌላውን እመን ለምን ትሉታላችሁ?

3) "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን ምሰሷቸውን ለማስረዳት ሲሉ የአዋልድ መጻሕፍትን ጉዳይ እንደ ዋና አቅጣጫ ማስለወጫና ማምለጫ ለመጠቀም ሞክረዋል። ይህም ብዙ ጊዜ የሚጠቀሙበት ስልት ነው። ሆኖም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ሐሳብ መሠረታዊ ጭብጡ አዋልድ መጻሕፍት አሉ የሉም? ለምንስ ይኖራሉ? ወይም አይኖሩም? የሚለው ሳይሆን፣ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ የሚለው ሐሳብ በራሱ መጽሐፍ ቅዱሳዊ ነው ወይስ አይደለም? የሚለውን መመርመር ነው። ስለዚህ የምሰሷቸውን ጸንቶ መቆም ሳያረጋግጡ ወደ አዋልድ መጻሕፍት ጉዳይ ሮጦ መግባት ጉዳዩን አቅጣጫ ለማስቀየር ካልሆነ በስተቀር ሌላ ፋይዳ የለውም። መጀመሪያ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን "ምሰሷችን" ያሉትን አስተምህሮ ከመጽሐፍ ቅዱስ እንዲያሳዩን እንፈልጋለን። ይህን ሳያሳዩን ግን ወደ ሌላ ጉዳይ የምንገባበት ምንም ምክንያት የለንም። ስለዚህ የዚህ ምዕራፍ ዐቢይ ጉዳይ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን ሐሳብ በራሱ በመጽሐፍ ቅዱስ ከተለያዩ አቅጣጫዎች መመርመር እንጂ ይህን ጉዳይ ትቶ ራሱን የቻለ ሌላ ጉዳይ ወደ ሆነው ወደ አዋልድ መጻሕፍት አጀንዳ መግባት አይደለም። ዋናው ጉዳይ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ነው።

4) በመቀጠልም **"የአበው የቀኖና መለኪያ"** በማለት እንደዚህ ብለዋል፡-

"የጥንት አባቶች አንድ መጽሐፍ ቀኖናዊ መሆኑን ወይም አለመሆኑን በሚከተሉት መለኪያዎች **እንደተጠቀሙ <u>ይታመናል</u>**፡-

1. ትንቢት ነው? ወይስ በእግዚአብሔር ሰው የተጻፈ ነው?
2. የመጽሐፉ ይዘት አስተማማኝና ሐቀኛ ነው ወይ? (አጠራጣሪ ሲሆን ገሸሽ ማለት የአበዎች ስልት ነበር።)

3. ጽሑፉ ልብ የሚነካና መንፈስን የሚቀሰቅስ ነው ወይ? (ሕይወት የመቀየር ኃይል አዝሏል ወይ?)

4. የቀደሙ የእግዚአብሔር ሰዎች ሲጠቀሙበት ቆይተዋል ወይ?

5. ይዘቱ የእግዚአብሔር ቃልነታቸው ከተረጋገጠላቸው ሌሎች መጻሕፍት ጋር የማይቃረንና የሚስማማ ነው ወይ? የሚሉ ጥያቄዎችን ያልመለሰና መመዘኛውን ያላሟሉ መጻሕፍት በመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት መካከል እንደ አንዱ መቆጠር አልቻሉም።" (ገጽ 240)

**አጭር ምልከታ በእነዚህ ሐሰቦች ላይ**

እስኪ ተሐድሶዎችን እነዚህን ጥያቄዎች እንጠይቃቸው፤

1. "የጥንት አባቶች አንድ መጽሐፍ ቀኖናዊ መሆኑን ወይም አለመሆኑን በሚከተሉት መለኪያዎች እንደተጠቀሙ **ይታመናል**" ስትሉ፣ **የሚታመነው** በእነ ማን ነው? ለምንስ እንዲያ ይታመናል? መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ እንደዚህ የሚል ነገር አለ? እንደዚህ የሚል ለመኖሩ የታወቀ በመሆኑ ከየት አመጣችሁት?

2. "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ካላችሁ፣ ለምን ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆኑ ሌሎች ሰዎችንም ሆነ ትምህርታቸውን ትጠቅሳላችሁ?

3. እነዚህ "የአበው ቀኖና መለኪያዎች" ያላችኋቸው ምንጫቸው ከየት ነው? መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ አሉ? ከሌሉ ግን (በእርግጥም የሉምና) ይህን ለመሰለ መሠረታዊ ነገር ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ ነገር ምስክር አድርጋችሁ ለምን ትጠቅሳላችሁ? ወይስ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው አስተምህሯችሁ ከልብ አታምኑበትም ማለት ነው? ምሰሷችሁ ጸንቶ መቆም የማይችል መሆኑን ራሳችሁ በተግባር እያረጋገጣችሁ እኮ ነው።

4. እነዚህን የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቀኖናዊ መሆን ወይም አለመሆን መለኪያ የሆኑ ቀኖናዎችን ያወጧቸው አባቶች በምን ሥልጣን እንደዚያ ማድረግ ቻሉ? የእነዚህን አባቶች ቀኖናዎች የምንቀበልበት ምክንያትስ ምንድን ነው? እነርሱ ተሳስተው ይሁን አይሁን በምን ማረጋገጥ እንችላለን?

5. "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የምትሉ እንደ መሆናችሁ፣ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ገብተው የሚቆጠሩትን መጻሕፍት ለመምረጥ እነዚህ ቀኖናዎች ለምን አስፈለጉ? አለዚያ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ የሚለው አስተምህሮ ፈረሰባችሁ ማለት ነው።

6. "ትንቢት ነው? ወይስ በእግዚአብሔር ሰው የተጻፈ ነው?" የሚለውን የመለኪያ ነጥብ ነው ወይም አይደለም ብሎ የሚያረጋግጠው ማን ነው? እንደዚያ እንዲወስንስ ሥልጣኑን ከየት አገኘው?

7. "የመጽሐፉ ይዘት እስተማማኝና ሐቀኛ ነው ወይም አይደለም አጠራጣሪ ነው" ብሎ የሚወስነው ግለሰብ ወይም አካል ማን ነው? ይህን የመወሰን ሥልጣኑንስ ከየት አገኘው?

8. "ጽሑፉ ልብ የሚነካና መንፈስን የሚቀስቅስ ነው ወይ?" የሚለው የመጻሕፍት ቀኖና መለኪያ ነበር ያላችሁት፣ እንደዚህ ያለ የቀኖና መለኪያ በቤተ ክርስቲያን ታሪክ ስለ መኖሩ ተሰምቶ ያውቃልን? ምንጩን ጠቅሳችሁልን ቢሆን ኖሮ ወደ ምንጩ ሂደን እናጣራ ነበር፣ ግን ምንጩ አልተጠቀሰልንም። ልብን መንካትና መንፈስን መቀስቀስ ዋና መመዘኛ ከሆነ፣ ከመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ባልተናነሰ ሁኔታ ልብን የሚነኩና መንፈስን የሚቀሰቅሱ ድርሰቶችና መጻሕፍት አይገኙም ይሆንን?

ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች ስለ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ያሏቸውን ሌሎች ተጨማሪ ሐሳቦች እና አጫጭር ምልከታዎችን እንመልከት፡-

- "የነገረ መለኮት ሊቅ የነበሩት ዶክተር ሉውስ ስፔር ቼፈር የመጽሐፍ ቅዱስ ልዩ መሆን ሲናገሩ፡- አስገራሚ ተያያዥነት ያላቸው 66 መጻሕፍት በአንድ ላይ መያዙና የተጻፈው ቃል ሁሉ በመንፈስ ቅዱስ ለመጻፉ ቋሚ ማስረጃ መኖሩ ነው ብለዋል።" (ገጽ 56)

  - "በመንፈስ ቅዱስ ለመጻፉ ቋሚ ማስረጃ መኖሩ" አሉ እንጂ ቋሚ ማስረጃ ያሉትን ማስረጃ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ አላሳያችሁንም።

- ". . . አሁን ግን የኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱሷን ከ66 መጻሕፍት ወደ 81 አሳድጋለች። በ1953 ዓ. ም የታተመውን መጽሐፍ ቅዱስ መለወጥ ለምን አስፈለገ?" (ገጽ 57)

  - በ1953 ዓ. ም የታተመው መጽሐፍ ቅዱስ አልተለወጠም። ተለወጠ ማለታችሁ ሐሰት ነው። ዋናው ነገር ግን እናንተ 66ቱን ከየት እንዳመጣችሁት ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ማሳየት ሳትችሉ፣ ሌላውን ለምን ይህን ያህል ተቀበልክ? ብላችሁ ለመጠየቅ አትችሉም።

- መጽሐፍ ቅዱስን የሚያትመው ወይም የሚያሳትመው አካል የሚያደርገው ነገር ቤተ ክርስቲያን መጻሕፍቱን ጨመረች ወይም ቀነሰች ሊያሰኝ ፈጽሞ አይችልም። በዚህ ከሆነስ፣ መጀመሪያ መጠየቅ ያለባችሁ ተሐድሶ ፕሮቴስታቶች ናችሁ። ምክንያቱም በ1455 ዓ. ም. ገደማ የማተሚያ መሣሪያን የሠራው ዮሐንስ ጉተንበርግ በሠራው መሣሪያ ለመጀመሪያ ጊዜ ያተመው መጽሐፍ **መጽሐፍ ቅዱስ** የነበረ ሲሆን፣ ያተመው መጽሐፍ ቅዱስ የያዛቸው መጻሕፍት ብዛትም 73 ነበር እንጂ 66 አልነበረም። ታዲያ እናንተ 7ቱን መጻሕፍት የት አደረሳችኋቸው?

- "የመጽሐፍ ቅዱስን ቁጥር በተመለከተ <u>አብዛኛው ዓለም</u> የእግዚአብሔር ቃል ብሎ 66 መጻሕፍትን ይዞ ሲገኝ የእኛ ቤተ ክርስቲያን ግን 81 መጻሕፍትን ይዛለች።" (ገጽ 59)

  - "አብዛኛው ዓለም" ማለት የትኛው ዓለም ነው? በምን ስሌት ደረሳችሁበት? የራስን ምኞት ትልቅ አስመስሎ ለማሳየት ከመመኘት የመነጨ አባባል ካልሆነ በቀር 66 መጻሕፍትን ብቻ የሚቀበለው የፕሮቴስታንቱ ዓለም ብቻ ነው። የካቶሊክ ቤተ ክርስቲያን የምትቀበለው መጽሐፍ ቅዱስ ብዛት 73 ነው፣ የምሥራቅ ኦርቶዶክስና የኦሬንታል አብያተ ክርስቲያንም አንዳንድ የቁጥር ማነስ መብዛት ሊኖር ቢችልም የሁሉም ግን ከ73 በላይ ነው። በዓለም የክርስቲያኖች አኃዝ መሠረት በብዛት አንደኛው የካቶሊክ ተከታዮች ናቸው። ስለዚህ "የመጽሐፍ ቅዱስን ቁጥር በተመለከተ <u>አብዛኛው ዓለም</u> የእግዚአብሔር ቃል ብሎ 66 መጻሕፍትን ይዞ ሲገኝ" የሚለው ሐሰት ነው። 73 መጻሕፍትን በሚቀበሉት በካቶሊኮች ላይ የምሥራቅ ኦርቶዶክስና የኦሬንታል ኦርቶዶክስ ሲደመሩ ደግሞ የዚህን አባባል ሐሰትነት የበለጠ ያጎሉታል።

- "የ81ዱ መጽሐፍ እንዲታተም ምክንያት የሆነው የፍትሐ ነገሥት መላምትን ዕውን ለማድረግ እንጂ የተካተቱት መጻሕፍት የካኖን መመዘኛ ስላሟሉ አይደለም።" (ገጽ 63)

  - "የካኖን መመዘኛ" የምትሉት ነገር ምንድን ነው? መመዘኛውን ያወጣውስ ማን ነው? በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ፣ "በእኔ ውስጥ ሊካተቱ የሚገባቸው መጻሕፍት መመዘኛቸው ይህ ነው" የሚል መግለጫ አለ? ልታሳዩንስ ትችላላችሁ? ከሌለ (በእርግጥም ስለሌለ) "የካኖን

መመዘኛ" የምትሉት ነገር ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ ነገር ነው ማለት ነው። ስለዚህ ይህ አባባል "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን ዋናውን የራሳችሁ ፈጠራ የሆነውን ምሰሶ፡ችሁን ገና ከጅምሩ አፈረሰባችሁ።

- "የአዲስ ኪዳንና የብሉይ ኪዳን ካኖን ከተጠናቀቀ ከ1700 ዓመታት በላይ ያለፈ ሲሆን የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ጉያ እንደ አሸን የፈሉ ድርሳናት ዛሬም ወደ መጽሐፍ ቅዱስነት እያደጉ እንደሆነ ማየት ለእኔ ከእግዚአብሔር የመራቃችን አንዱ ምልክት ነው ብዬ አምናለሁ። በየአገራቱ ያለው የዓለም አብያተ ክርስቲያናት የመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር የሚያሳትመው የመጽሐፍ ቅዱስ ነው? ወይስ በየአገራቱ ያሉት አብያተ ክርስቲያናት የሚያቀርቡለትን የተስማሙበትን መጽሐፍ ቅዱስ?" (ገጽ 63)

  - "በመጀመሪያ "የዓለም አብያተ ክርስቲያናት የተስማሙበት መጽሐፍ ቅዱስ" የሚባል "መጽሐፍ ቅዱስ" አለ ወይ? መቼ እና የት ነው የተስማሙት? ይኼ ሁሉ የተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች ግምታዊ ፈጠራ እንጂ እንደዚህ የሚባል የለም! የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ዝርዝርና ቁጥር በአብዛኛው አንድ ሲሆን፣ በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ረገድ ግን ሐዋርያዊ መሠረት ባላቸው አብያተ ክርስቲያን ዘንድ መጠነኛ ልዩነቶች አሉ። የኦርቶዶክስ አብያተ ክርስቲያን የሚቀበሏቸው የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ዝርዝርና ቁጥር የሮማ ካቶሊክ ከምትቀበላቸው በተወሰነ መልኩም ቢሆን ልዩነት አላቸው። ስለሆነም በኦርቶዶክሳውያን አብያተ ክርስቲያን ዘንድ ያለው የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቁጥርም በመሠረታዊ ደረጃ አንድ ሲሆን በየአብያተ ክርስቲያናቱ መጠነኛ ልዩነቶች አሉ። ከዚህ ውጭ ግን "የዓለም አብያተ ክርስቲያናት የተስማሙበትን መጽሐፍ ቅዱስ" የሚባል የለም።
  - እንዲሁም "የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ጉያ እንደ አሸን የፈሉ ድርሳናት ዛሬም ወደ መጽሐፍ ቅዱስነት እያደጉ ነው" የሚለው እንዲያው ሐሰት ብቻ ሳይሆን ነውርም ነው። ማንንም ቢሆን መተቸትና መንቀፍም እንኳ ቢያስፈልግ በሆነው ነው እንጂ ባልሆነው መተቸት ተገቢ አይደለም። እስኪ አንድ ማስረጃ አቅርቡ ቢባሉ ማቅረብ አይችሉም።

በቀሪው የዚህ ምዕራፍ ክፍል ላይ ይህንኑ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን የተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች "ምሰሶ" አንድ በአንድ እንመረምረዋለን። ከሁሉ አስቀድመን

ማየት የሚኖርብን ነገር ቢኖር ይህ አስተምህሯቸው መጽሐፍ ቅዱሳዊ ነው ወይስ አይደለም? የሚለውን ጉዳይ ነው።

## 1.3 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ("ሶላ ስክሪፕቱራ") መጽሐፍ ቅዱሳዊ ነውን?

ከሁሉ አስቀድሞ ሊጠየቅ የሚገባው ዋና ጥያቄ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ይላል? ወይስ አይልም? የሚለው ነው። በመጀመሪያ ፕሮቴስታንቶች መጽሐፍ ቅዱስ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ይላል ለማለት የሚያቀርቧቸውን ጥቅሶችና መከራከሪያዎች እንመልከታቸው። ዋና ምስክር አድርገው የሚጠቅሱት ጥቅስ ይህ ነው፡-

1. ". . . የእግዚአብሔር ሰው ፍጹምና ለበጎ ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ፣ የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ ለትምህርትና ለተግሣጽ፣ ልብንም ለማቅናት፣ በጽድቅም ላለው ምክር ደግሞ ይጠቅማል።" 2 ጢሞ. 3፡16-17

1) ይህ ጥቅስ ፕሮቴስታንቶች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ለሚለው አስተምህሯቸው ብቸኛው ሊባል በሚችል መልኩ ዋናው የመከራከሪያ ጥቅሳቸው ነው። ሆኖም ጥቅሱ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ በቂ ነው" ይላል ወይ? የሚለውን እንመልከት። ይህ ጥቅስ "የእግዚአብሔር ሰው ፍጹምና ለበጎ ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ፣ የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ . . . **ይጠቅማል** (is profitable)" ይላል እንጂ **"በቂ ነው፣ ሌላ አያስፈልግም"** (is sufficient) አይልም። ቅዱስ ጳውሎስ መልእክቱን የጻፈበት ቋንቋ ግሪክ ሲሆን ቁጥር 16 ላይ የተጠቀመው የግሪኩ ቃል ኦፌሊሞስ *(ophelimos)* የሚል ሲሆን ትርጉሙም "ጠቃሚ" ("useful") ማለት እንጂ "በቂ" ("sufficient") ማለት አይደለም። ጥቅሱ በማንኛውም ቋንቋ ቢተረጎም፣ መጽሐፍ ቅዱስ "ይጠቅማል" ይላል እንጂ "ብቻውን በቂ ነው" አይልም።

አንድ ነገር ጠቃሚ ነው ማለት "ብቻውን በቂ ነው" ማለት አይደለም። ለምሳሌ ውኃ ለሕይወታችን ጠቃሚ ነው ማለት ውኃ ብቻውን በቂ ነው ማለት ነውን? ምግብ ጠቃሚ ነው ማለት ምግብ ብቻ "በቂ ነው" ማለት ነውን? ወይስ አየር ለሕይወት ጠቃሚ ነው ማለት ከአየር በቀር ሌላ ነገር አያስፈልግም ማለት ነው ያሰኛልን? እንደዚሁም ሁሉ ቅዱስ መጽሐፍ ጠቃሚያችን ነው፣ አስፈላጊያችን ነው፤ ሆኖም ይህ ማለት ከእርሱ በስተቀር ሌላ ምንም ነገር አያስፈልግም ማለት ግን አይደለም። ለክርስቲያኖች ሕይወትና ትምህርት መጽሐፍ ቅዱስ የማይተካ ቦታ ያለው መሆኑ ግልጽና የታወቀ ነው፣ ሆኖም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ወደሚል ጽንፍ እንድንሄድ ግን ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ አይፈቅድልንም።

"የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ይጠቅማል" የሚለውን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ፣ ከእርሱ በቀር ሌላ አንዳችም ነገር አያስፈልግም" ማለት ነው የሚለውን ይህን የአተረጓጎም መርሕ በሌሎች የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶች ላይ እንተግብረውና ምን ማለት እንመልከት። ለምሳሌ በያዕቆብ መልእክት 1:4 ባለው ቃል ላይ ሲተገበር እስኪ እንመልከት፤

> **ትዕግሥትም** ምንም የሚጎድላችሁ ሳይኖር ፍጹማንና ምሉዓን ትሆኑ ዘንድ ሥራውን **ይፈጸም**። But let patience have her perfect work, that ye may be perfect and entire, wanting nothing. ያዕ. 1:4

ይህ ማለት፣ ትዕግሥት ካለኝ ፍጹምና ምሉዕ ስለሆንኩ ሌላ ምንም ነገር አያስፈልገኝም ማለት ነውን? "ትዕግሥት ብቻ" (Sola Patience) ማለት ያሰኛልን? ትዕግሥት ብቻ ፍጹምና ሙሉ ሰው ማድረግ የሚችል ከሆነስ ሌላ ነገር፣ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስም አያስፈልግም ማለት ነውን? ከትዕግሥት ውጭ ሌላ ነገር፤ ማለትም ጸሎት፣ ክርስቲያናዊ ኅብረት፣ በቃለ እግዚአብሔር መተናነጽና የመሳሰለው ሁሉ አላስፈላጊ ነው ማለት ነውን?

የ2 ጢሞ. 3:17 ሐሳብ መጽሐፍ ቅዱስ "ፍጹምና ለበጎ ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ እንዲሆን ያደርጋል" ማለቱ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን በቂ ነው፣ ሌላ አያስፈልግም" ማለት ነው የሚል ካለ፤ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ "ትዕግሥትም ምንም የሚጎድላችሁ ሳይኖር ፍጹማንና ምሉዓን ትሆኑ ዘንድ ሥራውን ይፈጽም" በማለት ትዕግሥት ፍጹምና ሙሉ ሰው እንደሚያደርግ አስረግጦ ይናገራል። ታዲያ ይህ ከሆነ "ትዕግሥት ብቻውን በቂ ነው፣ ከትዕግሥት በቀር ሌላ ምንም ነገር አያስፈልግም" ማለት ነው ያሰኛልን? ራሳቸው ፕሮቴስታንቶች እንኳ ይህን የአተረጓጎም መርሕ አይቀበሉትም። ምክንያቱም በዚህ አተረጓጎም ከሄድን ራሱ መጽሐፍ ቅዱስም ላያስፈልግ ነዋ! ታዲያ አንድን ነገር "ይጠቅማል" ማለት "ብቻውን በቂ ነው" ወደ ማለት የሚጠመዘዘው ለምንድን ነው? በእነርሱ የአተረጓጎም መርሕ እንሂድ ከተባለ 2 ጢሞ. 3:17 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ይላል ከሚሉት ይልቅ ያዕ. 1:4 እጅግ ግልጽና ጠንካራ በሆነ ሁኔታ "ትዕግሥት ብቻ" ይላል ለማለት ይቻል ነበር። ስለዚህ 2 ጢሞ. 3:17 መጽሐፍ ቅዱስ ራሱ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን በቂ ነው" እንደሚል አስመስለው የሚያቀርቡት አተረጓጎም መጽሐፉ የማይለውን በግድ ለራስ ሐሳብ እንዲመች አድርጎ የመጠምዘዝ ተግባር ነው።

እንደዚሁም ቅዱስ ጳውሎስ በኤፌሶን መልእክቱ ላይ የጻፈውን ቃል እንመልከት፦

> እርሱም አንዳንዶቹ ሐዋርያት፣ ሌሎቹም ነቢያት፣ ሌሎቹም ወንጌልን ሰባኪዎች፣ ሌሎቹም እረኞችና አስተማሪዎች እንዲሆኑ ሰጠ፤ ሁላችን የእግዚአብሔርን ልጅ

> በማመንና በማወቅ ወደሚገኝ አንድነት፣ ሙሉ ሰውም ወደ መሆን፣ የክርስቶስም ሙላቱ ወደሚሆን ወደ ሙላቱ ልክ እስከንደርስ ድረስ፣ ቅዱሳን አገልግሎትን ለመሥራትና <u>ለክርስቶስ አካል ሕንጸ **ፍጹማን** ይሆኑ ዘንድ</u>። ኤፌ. 4፡11-13

2 ጢሞ. 3፡16-17 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን በቂ ነው" ይላል ከተባለ፣ ኤፌ. 4፡11-13ም ክርስቲያኖችን ወደ ፍጹምነት ለመምራት "እረኞችና ሰባኪዎች ብቻ ይበቃሉ" ይላል ማለት ነዋ! በኤፌ. 4 ላይ ክርስቲያን በእምነቱ እንዲጸና፣ ሙሉ ሰው ወደ መሆንና ወደ ክርስቶስ ፍጹም ሙላት እንዲያድግ፣ እንዲሁም በትምህርት ነፋስ እንዳይፍገመገምና እንዲጸና በቤተ ክርስቲያን የማስተማር አገልግሎት እነዚህን ሁሉ ይታጠቃል። ክርስቲያኖችን በማጽናትና ወደ ክርስቶስ ፍጹም ሙላት በማድረስ ረገድ የዚህ ዐረፍተ ነገር አገላለጽ ከ 2 ጢሞ. 3፡16-17 ይልቅ በእጅጉ የጠነከረ ነው። ቅዱስ ጳውሎስ እዚህ ላይ ቅዱሳት መጻሕፍትን ፈጽሞ አላነሣቸውም። ሆኖም ግን ቅዱሳት መጻሕፍትን እዚህ ላይ በስም ስላልጠቀሳቸው ብቻ "አያስፈልጉም፣ ምክንያቱም የቤተ ክርስቲያን መምህራንና ትምህርታቸው ብቻ ይበቃሉና" ወደሚል የተሳሳተ ድምዳሜ ልንሄድ አይገባም። በአንድ አንቀጽ ላይ የአንድ የሆነ ነገር አለመጠቀስ ማለት ፈጽሞ የለም ወይም አያስፈልግም ማለት አይደለምና። የዚያ ነገር ጠቀሜታ መጠቀስ ማለትም ከእርሱ ብቻ በቀር ሌላ ነገር አያስፈልግም ማለት አይደለምና።

አንድ ሌላ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ጨምረን እንመልከት፡-

> ከእናንተ የሆነ የክርስቶስ ባሪያ ኤጳፍራ ሰላምታ ያቀርብላችኋል። በእግዚአብሔር ፈቃድ ሁሉ <u>ተረድታችሁና ፍጹማን ሆናችሁ እንድትቆሙ፣ ሁልጊዜ ስለ እናንተ በጸሎቱ ይጋደላል</u>። **ቆላ.** 4፡12

ታዲያ ይህ ማለት፣ የቆላስይስ ክርስቲያኖች "ፍጹማን ሆነው እንዲቆሙ" ኤጳፍራ የተባለው የቤተ ክርስቲያን አገልጋይ ሁል ጊዜ በጸሎቱ ስለ እነርሱ ስለሚጋደልላቸው፣ የኤጳፍራ ጸሎት ብቻ በቂ ነው፣ ከእርሱ ጸሎት ውጭ ሌላ ምንም ነገር አያስፈልጋቸውም ማለት ነውን? 2 ጢሞ. 3፡14-17ም እንደዚሁ ነው፤ ይጠቅማል ማለት "ብቻውን በቂ ነው"፣ "እርሱ ብቻ እንጂ ሌላ ነገር አያስፈልግም" ማለት አይደለም።

ይህ በግልጽ የሚያሳየው ነገር ቢኖር 2 ጢሞ. 3፡17 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የማይል መሆኑን ብቻ ሳይሆን ቅዱስ ጳውሎስ ይህን ወደማለት ትንሽ እንኳ የተጠጋ ነገር ያላለ መሆኑን ነው። ምክንያቱም ራሱ ቅዱስ ጳውሎስ "የተጻፈው ብቻ ነው፣ ከዚያ ውጭ አንዳችም ነገር አትጠቀም" ማለቱ ቢሆን ኖሮ በሌሎቹ መልእክቶቹ ያላቸውን ነገሮች ለጊዜው ብናቆያቸው እንኳ፣ እዚሁ መልእክቱ ላይ "ብዙ ሰዎች የመሰከሩለትን

**ከእኔም የሰማኸውን** ሌሎችን ደግሞ ሊያስተምሩ ለሚችሉ ለታመኑ ሰዎች አደራ ስጥ" (2 ጢሞ. 2፡2) በማለት ለጢሞቴዎስ በጽሑፍ ያልጻፈለትን፣ ግን በቃል ያስተማረውን ትምህርቱን እንዲይዝ፣ ለራሱ ብቻ ሳይሆን ለሌሎችም እንዲደርስ እንዲያደርግ፣ ለዚህም ደግሞ ሊያስተምሩ ለሚችሉ ሰዎች አደራ እንዲሰጥ እንዴት ይጽፍለት ነበር? ፕሮቴስታንቶች እንደሚሉት ከሆነ፣ ጢሞቴዎስ "አይ እኔ ከጻፍክልኝ ውጭ ሌላውን አልቀበልም" በማለት የቅዱስ ጳውሎስን ትእዛዝ መቃወም አለበት ማለት ነው!

ስለሆነም 2 ጢሞ. 3፡16-17 በምንም ሁኔታ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" አይልም። ቅዱሳት መጻሕፍትን ማንበብ አንድን ሰው ለመልካም ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ እንዲሆን ሊረዳው የሚችል መሆኑ እውነተኛ ነገር ነው። ሆኖም ይህ ማለት የሚያስፈልገው መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ነው ማለት ግን አይደለም። ይህ ጥቅስ ቅዱሳት መጻሕፍት ጠቃሚ መሆናቸውን ይገልጻል እንጂ "እነርሱ ብቻ" አይልም። ይህ አረዳዳቸው "ወይ ይህን፣ አለዚያ ያንን" ("Either/ Or") ዓይነት የሆነው የፕሮቴስታንቶች የተሳሳተ አስተሳሰብ ውጤትና ማሳያ ነው። ለአብነትም "ትውፊት ወይስ ድኅነት?" በሚል የተሐድሶ ፕሮቴስታንት መጽሐፍ ላይ "ድኅነት በማርያም ወይስ በኢየሱስ ክርስቶስ?"፣ "ድኅነት በመላእክት ወይስ በኢየሱስ ክርስቶስ?"፣ "ድኅነት በተክለ ሃይማኖት ወይስ በኢየሱስ ክርስቶስ?"፣ "ድኅነት በጾም ወይስ በኢየሱስ ክርስቶስ?" ብሎ እንደ እነርሱ አረዳድ መስሎት ለንጽጽር የማይቀርቡ ነገሮችን አነጻጽሮ አቅርቧል። (ትውፊት ወይስ ድኅነት?፣ 2005)[1]

2) በቁጥር 16 ላይ "የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት <u>መጽሐፍ</u> **<u>ሁሉ</u>** (πασά γραφή - pasa graphe) ለትምህርትና ለተግሣጽ ልብንም ለማቅናት በጽድቅም ላለው ምክር ደግሞ ይጠቅማል" በሚለው አንቀጽ ውስጥ **"ሁሉ"** ተብሎ የተተረጎመው ፓሳ (πασά - pasa) የሚለው የግሪክ ቃል <u>"እያንዳንዱ"</u> ማለት እንጂ <u>"ሁሉም"</u> ማለት አይደለም።[2] ይህም ማለት ከግሪክ በትክክል ሊተረጎም የሚገባው **"እያንዳንዱ መጽሐፍ"** ተብሎ እንጂ **"ሁሉም መጽሐፍ"** ተብሎ አይደለም። ስለሆነም ቃሉ የሚገልጸው በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያለውን እያንዳንዱን መጽሐፍ እና የእያንዳንዱን መጽሐፍ ጠቃሚ መሆን ነው። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ትምህርት እውነት ከሆነ፣ በቁጥር 16 መሠረት እያንዳንዱ የመጽሐፍ ቅዱስ መጽሐፍ በራሱ ብቻውን የእምነት መለኪያና መወሰኛ ሆኖ ሊወሰድ ነው ማለት ነው።

---

[1] ስለ ኦርቶዶክሳዊ የነገረ ድኅነት አስተምህሮ ለመረዳት፣ መድሎተ ጽድቅ - ቅጽ ፩ ከገጽ 66 – 218 መመልከት ይቻላል።

[2] The Interlinear Greek-English New Testament, George Ricker Berrry, Grand Raphids, Michigan, 1985, p. 552

ይህም ማለት ለምሳሌ የማቴዎስ ወንጌል ብቻውን፣ ወይም አራት ዘፍጥረት ብቻውን "በቂ" ነው ሊሰኝ ነው። እንዲህ ከሆነ ደግሞ ለምሳሌ የማቴዎስ ወንጌል ብቻውን በቂ ከሆነ፣ ሌሎቹ ወንጌሎች እና ሌሎቹ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት በሙሉ አያስፈልጉም ሊባል ነው። ዘፍጥረት ብቻውን በቂ ከሆነ ከዚያ ቀጥሎ ያሉት መጻሕፍት ሁሉም አላስፈላጊ ሊሆኑ ነው ማለት ነው። እንደዚህ ከሆነ ስለ ክርስትና ለማወቅ የሚበቃው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ሳይሆን "የማቴዎስ ወንጌል ብቻ"፣ ወይም "የዮሐንስ ወንጌል ብቻ" ወይም "የያዕቆብ መልእክት ብቻ" . . . ሊሆን ነው ማለት ነው! ምክንያቱም እያንዳንዱ መጽሐፍ "ጠቃሚ ነው" የሚለውን "በቂ ነው" ወደሚል የተሳሳተ አተረጓጎም እንውሰደው ከተባለ የሚያስከትለው ድምዳሜ እንደዚህ ያለ ነውና። ሆኖም ይህ ግልጽ ስህተት መሆኑ የታወቀ ነው።

እንደዚህ ከሆነ የአንዱ በቂነት ሌሎቹን፣ የሌሎቹም በቂነት አንዱን ያጠፋዋል። በመጨረሻም ምንም ጠቃሚ የሆነ መጽሐፍ እንዳይቀር ያደርጋል። ስለዚህ 2 ጢሞ. 3:16-17 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን እምነትና አስተምህሮ ሊያረጋግጥ ይቅርና እንደዚህ የሚል ገጸ ንባብም ሆነ ትርጉም የለውም። ቅዱስ ጳውሎስ በዚህ ጥቅስ ላይ የሚለው እያንዳንዱ የመጽሐፍ ቅዱስ መጽሐፍ የእግዚአብሔር ሰው ለመልካም ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ ይጠቅመዋል አለ እንጂ እያንዳንዱ መጽሐፍ በየራሱ በቂ ነው አላለም። ቅዱሳት መጻሕፍትን ልክ አንድ ድምፅ እንደሚሰጥ ዐሥር አውታር እንዳለው በገና በአንድነት መጠቀም ይገባል እንጂ ነጣጥሎ አንዱ መጽሐፍ ብቻ ማለት የማይታሰብ ነውና።

3) ሌላው ልብ ሊባል የሚገባው መሠረታዊ ነገር ደግሞ፣ ቅዱስ ጳውሎስ በዚህ ጥቅስ ላይ የሚናገረው ስለ ብሉይ ኪዳን መጻሕፍት እንጂ ስለ ሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት አለመሆኑ ነው። ምክንያቱም ቅዱስ ጳውሎስ ይህን መልእክቱን ለጢሞቴዎስ በሚጽፍለት ጊዜ (በ65 ዓ. ም. ገደማ) ሌሎቹ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ገና ተጽፈውና ተሰባስበው አላለቁም ነበር። ጢሞቴዎስ ሕፃን ሳለ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ገና አልተጻፉም ነበር። ስለዚህ ቅዱስ ጳውሎስ **"ቅዱሳት መጻሕፍት"** ብሎ የተናገረላቸው የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት እንጂ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት አይደሉም። ይህ ጥቅስ "ሶላ ስክሪፕቱራ - መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ይላል ማለት "ብሉይ ኪዳን ብቻ" ማለት ነው የሚሆነው።

ስለዚህ ቅዱስ ጳውሎስ በዚህ መልእክቱ ላይ "ቅዱሳት መጻሕፍት ብቻ" ብሏል ከተባለ ወይ የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትን ብቻ፣ ወይም ደግሞ ገፋ ቢል እንኳ እርሱ መልእክቱን እስከ ጻፈበት ዘመን የነበሩትን የተወሰኑ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን ብቻ የሚጨምር ነው ማለት ነው። ይህ ደግሞ ትክክል ሊሆን አይችልም! ይህ

አባባል የሚወስደው "ብሉይ ኪዳን ብቻውን ያለ ሐዲስ ኪዳን በቂ ነው" ወደ ማለት ነው። ምክንያቱም እንኳንስ በቀኖና ተለይተው ሊታወቁ ይቅርና ገና ያልተጻፉ መጻሕፍትን ጨምሮ "በቂ ናቸው" ብሏል ለማለት የሚያስችል አንዳችም ፍንጭም ምክንያትም የለምና።

ስለዚህ በዚህ የእነርሱ አተረጓጎም ከተሄደ ራሱ ሐዲስ ኪዳንም አላስፈላጊ ሊሆን ነው ማለት ነው! ስለሆነም ይህ ጥቅስ ተጠቃሽ ስለሆኑ አምላካውያት ምንጮች ወሰንና ገደብ ለማበጀት ጥቅም ላይ ይዋል ከተባለ ከጨዋታ ውጭ የሚሆነው ራሱ ይህ ጥቅስም ነው፤ መላው ሐዲስ ኪዳንም መውጣት ይኖርበታልና። ስለዚህ የክርስቲያኖች የእምነት ምንጭ መጽሐፍ ብሉይ ኪዳን ብቻ ይሆናል ማለት መሆኑ ነው። ይህ ደግሞ ክርስቲያን ነኝ የሚል ሁሉ የማይቀበለው ሐሳብ ነው። እንዲያው ከዚያም ቢገፋ እንኳ ከዚህ የቅዱስ ጳውሎስ መልእክት በኋላ የተጻፉ ሌሎች የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት (ለምሳሌ የዮሐንስ ወንጌልና ራእየ ዮሐንስ የተጻፉት ከ96-98 ዓ. ም ነበር) በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ገብተው አይቆጠሩም ማለት ሊሆን ነው! ስለዚህ ይህን ጥቅስ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ለሚለው ትምህርታቸው ማስረጃ አድርገው የሚጠቅሱ ወገኖች መጽሐፍ ቅዱስ እንዴትና መቼ እንደ ተጻፈ እና እንደ ተሰባሰበ ታሪኩንና ሂደቱን ከማወቅ "ነጻ" የሆኑ ሰዎች ናቸው። ቅዱስ ጳወሎስ ለጢሞቴዎስ የላከውን የመጀሪያ መልእክቱን የጻፈው በ 63 እና 65 ዓ. ም. መካከል እንደሆነ ይነገራል።

4) 2 ጢሞ. 3፥16-17ን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ይላል ማለት ከዐውዱ ውጭ ለመተርጎም መሞከር ነው። እነዚህን ጥቅሶች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ይላል ለማለት የሚጠቅሷቸው ወገኖች ብዙውን ጊዜ ከኋላ ያሉትን ጥቅሶች (ቁጥር 14 እና 15ን) ያልፏቸዋል ወይም አያነሷቸውም። ምክንያቱም ቁጥር 14 እና 15 ላይ ከተጻፈው ሐሳብ ጋር ቁጥር 16 እና 17ን አብረን ብናነባቸው ሐሳቡን በትክክለኛው ዐውድ እንድንረዳው ስለሚረዳን ነው። ስለዚህ ከቁጥር 14 ጀምሮ እንመልከታቸው፡-

14. አንተ ግን በተማርህበትና በተረዳህበት ነገር ጸንተህ ኑር፣ ከማን እንደ ተማርኸው ታውቃለህና፤

15. ከሕፃንነትህም ጀምረህ ክርስቶስ ኢየሱስን በማመን፣ መዳን የሚገኝበትን ጥበብ ሊሰጡህ የሚችሉትን ቅዱሳን መጻሕፍትን አውቀሃል።

16-17 የእግዚአብሔር ሰው ፍጹምና ለበጎ ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ፣ የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ ለትምህርትና- ለተግሣጽ ልብንም ለማቅናት በጽድቅም ላለው ምክር ደግሞ ይጠቅማል።

ቅዱስ ጳውሎስ ጢሞቴዎስን "በተማርህበትና በተረዳህበት ነገር ጸንተህ ኑር" (ቁ. 14) ሲለው እንጂ የተማርከውን ተወውና የተጻፈልህን ብቻ ተከተል አላለውም። ጢሞቴዎስ ክርስቶስ ኢየሱስን እንዲያምን የተማረው ከመጽሐፍ ብቻ አይደለም፣ ከራሱ ከቅዱስ ጳውሎስም በቃሉ ተምሯል እንጂ።

ቅዱስ ጳውሎስ በዚህ መልእክቱ ላይ እንደ ገለጸው፣ ጢሞቴዎስን "ፍጹምና ለበጎ ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ" እንዲበቃ የሚረዱት ሦስት (3) ምንጮች አሉ ማለት ነው፤ እነዚህም፡-

- ከሕፃንነቱ ጀምሮ ያገኘው መልካም ክርስቲያናዊ አስተዳደግ፣
- ከቅዱስ ጳውሎስ ከሕይወቱ በማየትና ከቃሉ በመስማት ያገኘው ትምህርት፣ እና
- ቅዱሳት መጻሕፍት ናቸው።

ለዚህ ዓላማ፣ ማለትም ጢሞቴዎስን "ፍጹምና ለበጎ ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ ይሆን ዘንድ" ለማድረግ ጠቃሚ የሆኑ ሌሎች ነገሮችም መኖራቸውን ቅዱስ ጳውሎስ በዚሁ መልእክቱ ላይ ጽፏል። ለአብነትም በ2 ጢሞ. 2፡19 እና 21 ላይ እንዲህ ብሏል፡-

> . . . የጌታን ስም የሚጠራ ሁሉ ከዐመፅ ይራቅ የሚለው ማኅተም ያለበት የተደላደለ የእግዚአብሔር መሠረት ቆሟል። በትልቅም ቤት የእንጨትና የሸክላ ዕቃ ደግሞ አለ እንጂ የወርቅና የብር ዕቃ ብቻ አይደለም፣ እኵሌቶቹም ለክብር፣ እኵሌቶቹም ለውርደት ይሆናሉ፤ **እንግዲህ ማንም ራሱን ከእነዚህ ቢያነጻ፣ ለክብር የሚሆን የተቀደሰም፣ ለጌታውም የሚጠቅም፣ <u>ለበጎም ሥራ ሁሉ የተዘጋጀ</u> ዕቃ ይሆናል።**

ስለዚህ በዚህ 2 ጢሞ. 2፡14-17 ላይ ተጽፎ የምናገኘው መልእክት ጢሞቴዎስ በክርስቶስ ኢየሱስ እንዲያምን የተማረባቸው ምንጮች ቅዱሳት መጻሕፍት ብቻ ሳይሆኑ ቅዱስ ጳውሎስ በቃሉ ያስተማረው ትምህርትም (ሐዋርያዊ ትውፊትም) መሆኑን ነው። ስለዚህ ቁጥር 16 እና 17ን ብቻ መጥቀስና "መጽሐፍ ብቻ" ይላል ማለት ትውፊትን የሚያመለክቱትን ከኋላ ያሉትን ጥቅሶች ሆን ብሎ መተውና በመጽሐፍ ቅዱስ ሽፋን የሚፈልጉትን የራስን ሐሳብ በሰዎች ላይ ለመጫን መሞከር ነው።

**5) "የእግዚአብሔር ቃል" የሚለው ሐረግ፣ የቃል ትምህርትንም የሚወክልና የሚገልጽ እንጂ የተጻፈን ትምህርት ብቻ የሚገልጽ አይደለም።**

በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ "የእግዚአብሔር ቃል" የሚለው አገላለጽ የሚያመለክተው የተጻፈ ቃልን ብቻ ሳይሆን የነቢያትንም ሆነ የሐዋርያትን የቃል ስብከትም የሚመለክት አገላለጽ ነው። ለምሳሌም በትንቢተ ኤርምያስ

ላይ እንዲህ የሚል እናገኛለን፡-

> ከይሁዳ ንጉሥ ከኢዮስያስ ከ13ኛው ዓመት ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ ባሉት በእነዚህ በ23ቱ ዓመታት፣ **<u>የእግዚአብሔር ቃል</u>** ወደ እኔ መጣ፣ እኔም ማልጄ ተነሥቼ **<u>ተናገርኋችሁ</u>**፣ ነገር ግን አልሰማችሁም። . . . ኤር. 25:3፣ 7-8

በኤርምያስ አፍ የተነገረው ያ የእግዚአብሔር ቃል ሁሉም ያልተጻፈ ቢሆንም፣ ግን የእግዚአብሔር ቃል ነው። ነቢዩ ኤርምያስ በ23ቱ ዓመታት የሰማውን የእግዚአብሔርን ቃል "ተናገርኋችሁ" አለ እንጂ "ጻፍኩላችሁ" አላለም። ነቢዩ መጽሐፍ መጻፉ ይታወቃል፣ ሆኖም የሰማሁትን ሁሉ ጽፌላችኋለሁ ግን አላለም። በኤርምያስ 1:7 ላይ እግዚአብሔር ኤርምያስን "የማዝዝህንም ሁሉ <u>ትናገራለህና</u>" አለው እንጂ "ትጽፋለህና" አላለውም።

በሐዋርያት ስብከትም እንደዚሁ ነው። ይልቁንም በሐዋርያት ሥራና በመልእክታት ላይ የምናገኛቸው "የእግዚአብሔር ቃል" ወይም "የጌታ ቃል" የሚሉት ሐረጎች የሚገልጹት የተጻፈ መጽሐፍን ሳይሆን የቃል ስብከትን ነው። ለምሳሌም ቅዱስ ጳውሎስ እንዲህ ያለውን እንመልከት፡-

> ስለዚህም ከእኛ <u>የሰማችሁትን</u> <u>የእግዚአብሔርን ቃል</u> ከእኛ በተቀበላችሁ ጊዜ፣ በእውነት እንዳለ በእናንተ በምታምኑ ደግሞ እንደሚሠራ <u>እንደ እግዚአብሔር ቃል</u> እንጂ እንደ ሰው ቃል አድርጋችሁ አልተቀበላችሁትም። 1 ተሰ. 2:13

ሐዋርያው "ከእኛ <u>የሰማችሁትን</u> <u>የእግዚአብሔርን ቃል</u>" አለ እንጂ "<u>የጻፍኩላችሁን</u> የእግዚአብሔር ቃል" አላለም፣ ያልተጻፈውና በቃሉ ያስተማራቸው ትምህርትም የእግዚአብሔር ቃል ነውና።

በሙሴ ዘመን እንኳ በመጽሐፍ የተጻፈው ቃል ያልተጻፈውን ቃል ሙሉ በሙሉ እንዲቀር አላደረገውም። ለምሳሌም 2 ሳሙ. 23:2፣ ኢሳ. 59:1፣ እና ኤር 1:9 ላይ በነቢያቱ አፍ ውስጥ ያለውን ወይም በአፋቸው የተነገረውን "የእግዚአብሔር ቃል" ሲል ገልጸታል።

የእግዚአብሔር ቃል በቃል ትውፊት መልኩ በተለያዩ ሰዎች ከትውልድ ወደ ትውልድ ይተላለፍ እንደ ነበር ብሉይ ኪዳንም ያስረዳናል። ለአብነትም ይህን እንመልከት፡-

> ይህንም ትእዛዝ እግዚአብሔር በነቢያቱ እጅ አዝዟልና፣ እንደ ዳዊትና እንደ ንጉሡ ባለ ራእይ እንደ ጋድ፣ እንደ ነቢዩም እንደ ናታን ትእዛዝ፣ ጸናጽልና በገና መሰንቆም አስይዞ [ንጉሥ ሕዝቅያስ] ሌዋውያንን በእግዚአብሔር ቤት አቆመ። 2 ዜና 29:25

ከዚህ ምን እንረዳለን?

(1) ንጉሥ ሕዝቅያስ ይህን ባደረገበት ጊዜ ዳዊት፣ ጋድና ናታን ከሞቱ ከ250 ዓመት በላይ ሆኗቸው ነበር።

(2) ሆኖም የቤተ መቅደሱን ሥርዓተ አምልኮ አፈጻጸም በተመለከተ እነዚህ የእግዚአብሔር ነቢያት (ዳዊት፣ ጋድና ናታን) ከእግዚአብሔር የተቀበሉትን ትእዛዝ (ይህንም ትእዛዝ - እግዚአብሔር በነቢያቱ እጅ አዝዟልና - ብሎ ገልጾታል) በቃል ትውፊት አስተላልፈው ነበር።

(3) ይህ የቤተ መቅደሱን ሥርዓተ አምልኮ የተመለከተው የእግዚአብሔር ትእዛዝ በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ አንድም መጽሐፍ ላይ ተጽፎ አይገኝም።

ይህ በግልጽ የሚያስረዳው ነገር "መጽሐፍ ብቻ" የሚለውን አስተምህሮ ብሉይ ኪዳን ውድቅ የሚያደርገው መሆኑን ነው። ምክንያቱም ንጉሡ ሕዝቅያስ በጽሑፍ ላይ የሌለ፣ ሆኖም ግን በትውፊት በተላለፈለት የአምልኮ ሥርዓት መሠረት ሌዋውያን በእግዚአብሔር ፊት እንዲቆሙ አድርጓልና።

እንደዚሁም በ 2 ዜና 35:4 ላይ እንዲህ ይላል:-

> የእስራኤልም ንጉሥ ዳዊት እንደ ጻፈው ልጁም ሰሎሞን እንደ ጻፈው በየሰሞናችሁና በየአባቶቻችሁ ቤቶች ተዘጋጁ፤ . . .

ሆኖም በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ ንጉሥ ዳዊትም ሆነ ልጁ ሰሎሞን፣ በየሰሞናቸውና በየአባቶቻቸው ቤቶች ተዘጋጅተው ማገልገልን በተመለከተ የጻፉት ነገር አናገኝም:: ይህም በትውፊት የመጣ ነው:: ይህን የመሰሉ ሌሎች የብሉይ ኪዳን አንቀጾችም ይህንኑ የነቢያትንና የባለ ራእዮችን በቀኖና በታወቁት መጻሕፍት ውስጥ ያልተጻፈ ትውፊት የሚጠቅሱ አሉ:: 2 ዜና 33:18-19 ፤ ኢሳ. 30:10 ፤ ኤር. 26:18 ፤ ዘካ. 1:4-6

በብሉይ ኪዳን ዘመን ሕጉ በመጽሐፍ ተጽፎ ከተሰጠ በኋላ የነበሩት እስራኤላውያን በተጻፈው ብቻ ኑሩ የተባሉ ሳይሆን፣ ሕዝቡ ካህናቱንና ፈራጆች ሆነው የሚሾሙትን ሰዎች ይሰሙ ዘንድ ታዝዘው ነበር። ይህን በተመለከተ እግዚአብሔር እንዲህ ሲል አዝዟል:-

> በደምና በደም፣ በፍርድና በፍርድ፣ በመቍሰልና በመቍሰል መካከል በአገርህ ደጅ ውስጥ ሰዎች ስለሚከራከሩበት ክርክር የሚሳንህ የፍርድ ነገር ቢነሣ፣ አንተ ተነሥተህ አምላክህ እግዚአብሔር ወደ መረጠው ስፍራ ትወጣለህ፤ ወደ ሌዋውያን ካህናት በዚያም

ዘመን ወደ ተሾመው ፈራጅ መጥተህ ትጠይቃለህ፤ እነርሱም የፍርዱን ነገር ይነግሩሃል። እግዚአብሔር በመረጠው ስፍራ የነገሩህን የፍርድ ነገር ታደርጋለህ፤ እንዳስተማሩህም ታደርግ ዘንድ ጠብቅ። . . . ማናቸውም ሰው ቢኰራ፥ በዚያም አምላክህን እግዚአብሔርን ለማገልገል የሚቆመውን ካህኑን ወይም ፈራጁን ለመስማት ባይወድድ፥ ያ ሰው ይሙት፤ . . . ዘዳ. 17፥8-13

በ2 ዜና 19፥6-11 ላይም ይህን የመሰለ ነገር እናገኛለን። በየዘመናቱ የነበሩ ሌዋውያንና ካህናት የክህነት አገልግሎታቸውን አፈጻጸም በተመለከተ የሚማሩት ከእነርሱ በፊት ከነበሩት በቃል ትውፊት አማካይነት ነበር እንጂ እያንዳንዳቸው የመጽሐፍ ቅዱስ ቅጂ እየያዙ ያንን ብቻ እያጠኑ አልነበረም። ቅዱሳት መጻሕፍትን ለሕዝቡ የሚተረጒሙትም ካህናቱ ነበሩ እንጂ እያንዳንዱ ሰው በግሉና በየቤቱ አልነበረም። 2 ዜና 15፥3

ስለዚህ የእግዚአብሔር ቃል ማለት የተጻፈው ብቻ ሳይሆን በቃል የተነገረውና በትውፊት ያለውም መሆኑን መጽሐፍ ቅዱስ ይገልጻል። ኢሳይያስ 1፡10 ላይም "የእግዚአብሔርን ቃል ስሙ" ይላል እንጂ "አንብቡ" አይልም። ሕዝቅኤል 33፡30 ላይም "የሕዝብህ ልጆች በቅጥር . . . እርስ በርሳቸውም . . . እንሂድና እግዚአብሔር ያለው ቃል ምን እንደ ሆነ እንስማ ብለው ይናገራሉ" ይላል። ስለዚህ ራሱ የመጽሐፍ ቅዱሱ ቃል ሕዝቡን በመንፈስ ቅዱስ ሆነው ወደ ተናገሯቸው ቃሎች ይመራል እንጂ ወደ ተጻፉት ብቻ ሂዱ አይልም።

6) **ራሱ ቅዱስ ጳውሎስ በመጻሕፍት ያልተጻፉና በትውፊት የተገኙ ነገሮችን ተጠቅሟል።**

ሀ) በ1 ቆሮ. 10፡4 ላይ እስራኤላውያንን በሲና በረሓ ውኃ ያጠጣቸውን ዐለት፥ "ይከተላቸው የነበረው መንፈሳዊ ዐለት" ብሎታል፥ በብሉይ ኪዳን ውስጥ አንድም ቦታ ላይ እስራኤላውያንን በሚሄዱበት ሁሉ ይከተላቸው ስለነበረው ስለዚህ ተአምራዊ ዐለት የተጻፈ ነገር የለም። ሆኖም የአይሁድ መምህራን ግን ይህ የቃል ትውፊት ነበራቸው። ቅዱስ ጳውሎስ በዚህ መልእክቱ ላይ የጻፈው ከአይሁድ የቃል ትውፊት ያገኘውን እውቀት ነው።

ለ) በ2 ጢሞ. 3፡8 ላይ ሙሴን የተቃወሙትን የግብጽ ጠንቋዮች ስም "ኢያኔስና ኢያንበሬስም ሙሴን እንደ ተቃወሙት" በማለት ስማቸውን ጽፏል። ሆኖም በየትኛውም የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ አንድም ቦታ ላይ የግብጽ ጠንቋዮች ስም ኢያኔስ እና ኢያንበሬስ እንደሚባል አልተጻፈም። ሆኖም



7) **ሌሎች**

ከዘመኑ ሐዋር

የአይሁድ ትውፊ

የሚቃረኑትንና

ደግሞ ተጠቅማ

3 Fr Tadros Malaty,

ቅዱስ ጳውሎስ ከትውፊት ባገኘው መሠረት ስማቸውን ጻፈልን። ስለዚህ ከዚህና ይህን ከመሰሉት አጠቃቀሶቹ እንደምንረዳው ቅዱስ ጳውሎስ ያለውን ብቻ ሳይሆን በእነዚያ የሌሉ ሆኖም በትውፊት የተገኙትን ደጋግሞ ጠቅሷቸዋል፤ እውቅናም ሰጥቷቸዋል ማለት ነው። ታዲያ ሌላ ነገር አያስፈልግም ማለቱ ቢሆን ኖሮ፣ በዚሁ መልእክቱ በዚሁ ምዕራፍ ላይ "ኢያኔስና ኢያንበሬስም ሙሴን እንደ ተቃወሙት" በማለት ለምን በመጽሐፍ ያልተጻፈ ነገር ተጠቀመ?

ሐ) በሐዋርያት ሥራ ላይ ለኤፌሶን ካህናት በተናገራቸው የስንብት ምዕዳን ላይ ". . . እርሱ ራሱ ከሚቀበል ይልቅ የሚሰጥ ብፁዕ ነው እንዳለ የጌታን የኢየሱስን ቃል ልታስቡ ይገባችሁ ዘንድ በሁሉ አሳየኋችሁ" ብሏል። (የሐዋ. 20፡35) ጌታችንና አምላካችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ እንደዚህ የሚል ቃል ስለመናገሩ በአራቱም ወንጌል ላይም ሆነ በሌሎቹ የሐዋርያት መልእክቶች ላይ አንድም ቦታ ላይ ተጽፎ አናገኝም። ስለዚህ ቅዱስ ጳውሎስ ይህን የጌታችንን ትምህርት ያገኘው ከትውፊት ነው እንጂ ከሌላ ከየት አገኘው ሊባል ይችላል?

በዮሐ. 21፡25 በተጻፈው መሠረት መጽሐፍ ቅዱስ ጌታችን ያስተማረውን ትምህርትና ያደረገውን ሁሉ የጻፈ አለመሆኑ ግልጽ ነው፡፡ ቅዱስ ጳውሎስ የጠቀሰው ይህ የጌታችን ትምህርት ለዚህ ጥሩ ማሳያ ነው፡፡ እርሱ መልእክቱን የሚልክላቸው ሰዎች በወንጌል ያልተጻፉ የጌታችን ትምህርቶችን ሊቀበሏቸው የማይገባ ቢሆኑ ኖሮ ለምን እንዲህ ብሎ ያስተምራቸው ነበር? ምክንያቱም ይህን ማድረጉ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ለሚለው አስተምህሮ ተቃራኒ ነውና፡፡

## 7) **ሌሎች ሐዋርያትም ትውፊትን ተጠቅመዋል።**

ከዘመነ ሐዋርያት አንሥቶ ቤተ ክርስቲያን መልካምና ጤነኛ የሆነውን የአይሁድ ትውፊት ሙሉ በሙሉ ውድቅ አላደረገችውም። የእግዚአብሔርን ቃል የሚቃረኑትንና ፈሪሳውያን ሠራሽ የሆኑትን በመተው መልካምና እውነት የሆኑትን ደግሞ ተጠቅማባቸዋለች።[3]

[3] Fr Tadros Malaty, The Orthodox Concept;TRADITION AND ORTHODOXY, P. 42

ለምሳሌም ቅዱስ ይሁዳ በመልእክቱ ላይ በሊቀ መላእክት በቅዱስ ሚካኤልና በዲያብሎስ መካከል ስለ ተካሄደው ክርክር "የመላእክት አለቃ ሚካኤል ግን ከዲያብሎስ ጋር በተከራከረ ጊዜ ስለ ሙሴ ሥጋ ሲነጋገር፡- ጌታ ይገሥጽህ አለው እንጂ የስድብን ፍርድ ሊናገረው አልደፈረም" ብሎ ጽፎልናል (ይሁዳ 9)። ይህ ግን በብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ አንድም ቦታ ላይ ተጽፎ አይገኝም፤ ሐዋርያው ከቃል ትውፊት ያገኘውን ጻፈልን እንጂ። እንደዚሁም ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ "ዳሩ ግን ለጣዖት የታረደውን እንዲበሉና እንዲሴስኑ በእስራኤል ልጆች ፊት ማሰናከያን ሊያኖርባቸው ባላቅን ያስተማረ የበለዓምን ትምህርት የሚጠብቁ በዚያ ከአንተ ጋር ስላሉ፤ የምነቅፍብህ ጥቂት ነገር አለኝ" በማለት የበለዓም ትምህርት ምን እንደነበረ ጽፏል። ራእ. 2፡14 ይህም እንዲሁ ከቃል ትውፊት የተገኘ ነው።

ይህንኑ የበለዓምን ጉዳይ በተመለከተ ቅዱስ ጴጥሮስ (2 ጴጥ. 2፡15) እና ቅዱስ ይሁዳም (ቁ. 11) ጽፈዋል። ሦስቱም ሐዋርያት አባቶቻችን የጻፉት በብሉይ ኪዳን ያልተጻፈውን. በለዓም የባላቅን የፀመየ ደመወዝ ለማግኘት ሲል እስራኤላውያንን በተንኮል እንዲጠመዱ ያደረገ መሆኑን - በሚገልጽ ሁኔታ ነው። ይህም ከቃል ትውፊት የተገኘ ነው።

8) **ጌታችንም ትውፊትን ተጠቅሟል።**

   ሀ) በማቴ. 2፡23 ላይ "በነቢያት፣ ናዝራዊ ይባላል የተባለው ይፈጸም ዘንድ፣ ናዝሬት ወደምትባል ከተማ መጥቶ ኖረ" የሚለው ቃል በብሉይ ኪዳን ካሉ የነቢያት ትንቢት መጻሕፍት ውስጥ በየትኛቸውም ውስጥ አይገኝም። ስለሆነም "የእግዚአብሔር ቃል" ተብሎ እውቅና የተሰጠው ይህ የነቢያት ትንቢት በመጻሕፍት ተጽፎ ሳይሆን በቃል ይተላለፍ የነበረ ነው ማለት ነው። ጌታችን "ናዝራዊ ይባላል" ተብሎ የተነገረውን ትንቢት የፈጸመው በትውፊት የሚገኘውን ነው።

   ለ) በማቴ. 23፡2-3 ላይ ጌታችን ጻፎችና ፈሪሳውያን በተመለከተ ሲያስተምር፣ ጻፎችና ፈሪሳውያን "በሙሴ ወንበር" ላይ የተቀመጡ ከመሆናቸው የተነሣ ሕጋዊና ሊታዘዙለት የሚገባ ሥልጣን ያላቸው መሆኑን አስተምሯል። ሆኖም ይህ "የሙሴ ወንበር" የሚለው መጠሪያ ቃልም ሆነ ሐሳብ በብሉይ ኪዳን ውስጥ አንድም ቦታ ላይ ተጽፎ አይገኝም። ይህ የሚገኘው ከሙሴ ጀምሮ የሚቆጠረውን የሕጉን መምህራን የተዋረድ ሐረግ በሚያስተምረው በአይሁድ የቃል ትውፊት (ሚሽናህ) ውስጥ ነው።

ስለዚህ መድኃኒታችን በናዝሬት ምኵራብ ተገኝቶ መጽሐፈ ኢሳይያስን በማንበብ መጻሕፍትን ማንበብን በተግባር እንዳሳየን ሁሉ፣ ትውፊትን በመጥቀስም እንደ አስፈላጊነቱ ትውፊትንም እንድንጠቀም አስተምሮናል። ቅዱስ ጳውሎስም፣ ቅዱስ

ዮሐንስም፣ ቅዱስ ጴጥሮስም፣ ቅዱስ ይሁዳም፣ ሌሎች ሐዋርያትም፣ ጌታችንም፣ "የተጻፈ ብቻ" ያሉ ሳይሆን ትውፊትንም ተጠቅመዋል። ስለዚህ የመጀመሪያዋ ቤተ ክርስቲያንና አባቶች በ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ - ሶላ ስክሪፕቱራ" አልተመሩም። ይህ ከጌታችንም ከሐዋርያትም አስተምህሮና መንፈስ የወጣ ሰው ሠራሽ የፈጠራ ትምህርት ነው።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ "ሰው ሠራሽ ትምህርት" (ማቴ. 15፡ 1-9፤ ቆላ. 2፡8) በመሆኑ እግዚአብሔርን በእውነት በሚፈልጉና መጽሐፍ ቅዱስን ሐዋርያዊ በሆነው የክርስትና መንፈስ ለመረዳት በሚሹ በሁሉም ሰዎች ዘንድ ውድቅ ሊደረግ ይገባዋል።

በየትኛውም የመጽሐፍ ቅዱስ ጽሑፍ ላይ የተጻፈው ብቻ በቂና ሌላ ነገር የማያስፈልገው ነው የሚል ነገር የለም። እንኳንስ በቀጥታ እንደዚያ ሊባል ቀርቶ በፍንጭ መልክ እንኳ የተገለጸ ነገር የለም። እንደዚሁም የተጻፈው ትምህርት በቃል የተነገራቸውንና የተማሩትን ትምህርት ሙሉ በሙሉ ይተካዋል፣ ከዚያ በኋላ የቃል ትውፊት ያቆማል ተብሎ የተጻፈም አንድም ቦታ ላይ የለም። 2 ተሰ. 2፡15 ፤ 2 ጢሞ. 1፡13፤ 2፡2፤ 1 ተሰ. 2፡13 ፤ ዕብ. 13፡7፡17፤ 2 ዮሐ. 12፤ 3 ዮሐ. 13

ራሳቸው ሐዋርያት የጻፉት በአጭሩ እንጂ ሁሉንም የክርስትና አስተምህሮ ከመነሻ እስከ መድረሻ ዘርዝረውና ጨርሰው የጻፉ አለመሆናቸውን ገልጸዋል። ቅዱስ ጳውሎስ በኤፌሶን መልእክቱ ላይ "አስቀድሜ በአጭሩ እንደ ጻፍሁ" በማለት ይህን ገልጿል። ኤፌ. 3፡3 በዕብራውያን መልእክቱ ላይም "ወንድሞች ሆይ፣ የምክርን ቃል እንድትታገሡ እመክራችኋለሁ፣ በጥቂት ቃል ጽፌላችኋለሁና" ብሏል። ዕብ. 13፡22 ቅዱስ ጴጥሮስም የመጀመሪያ መልእክቱን ሲያጠቃልል "...በአጭሩ ጽፌላችኋለሁ" ብሏል። 1 ጴጥ. 5፡12 ቅዱሳን ሐዋርያት በመልእክቶቻቸው ላይ፣ የጻፏቸው መልእክቶቻቸው ለቤተ ክርስቲያን የሚያስፈልጓት ብቸኛዎቹ የሃይማኖት መመሪያዎች እነዚያ ብቻ ስለመሆናቸው አንድም ፍንጭ የለም።

2. ማስረጃዎቻችን ናቸው የሚሏቸው ሌሎቹ ጥቅሶች ደግሞ እነዚህ ናቸው፡-

   እኔ ያዘዝኋችሁን የአምላካችሁን የእግዚአብሐርን ትእዛዝ ትጠብቃላችሁ እንጂ ባዘዝኋችሁ ቃል ላይ አትጨምሩም፣ ከእርሱም አታጎድሉም። ዘዳ. 4፡2 **እና**

   በዚህ መጽሐፍ የተጻፈውን የትንቢት ቃል ለሚሰማ ሁሉ እኔ እመሰክራለሁ፤ ማንም በዚህ ላይ አንዳች ቢጨምር እግዚአብሐር በዚህ መጽሐፍ የተጻፉትን መቅሠፍቶች ይጨምርበታል፤ ማንምም በዚህ በትንቢት መጽሐፍ ከተጻፉት ቃሎች አንዳች ቢያጎድል፣ በዚህ መጽሐፍ

ከተጻፉት ከሕይወት ዛፍና ከቅድስቲቱ ከተማ እግዚአብሔር ዕድሉን ያጎድልበታል። ራእ. 22፥18-19

እነዚህ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች በግልጽ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ብለዋል ሲሉ ይከራከራሉ። ሆኖም የዚህ ሐሳብ ችግሮቹ ብዙ ናቸው፤

1) የመጀመሪያውን ጥቅስ (ዘዳ. 4፥2) ፕሮቴስታንቶች እንደሚሉት እንተርጉመው ከተባለ፣ ከብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ውጭ ሌሎች መጻሕፍት (የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት) ሊኖሩ አይችሉም ማለት ነው። ምክንያቱም ሙሴ "ባዘዝኋችሁ ቃል ላይ አትጨምሩም" ያለው ከእርሱ በኋላ (ከኦሪት ዘዳግም በኋላ) ምንም ነገር እንዳትጨምሩ ማለቱ ነው ከተባለ፣ ከኦሪት ዘዳግም በኋላ የተጻፉት ሌሎች የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት (መጽሐፈ ኢያሱ፣ መጽሐፈ መሳፍንት፣ መጽሐፈ ሩት፣ . . . ትንቢተ ኢሳይያስ፣ . . .) በሙሉ አያስፈልጉም ማለት ነው ያስኛል። በዚያውም ላይ "ባዘዝኋችሁ ቃል ላይ" አለ እንጂ "በጻፍኩላችሁ ቃል ላይ" አላለም። ምክንያቱም መሠረታዊውና ዋና ዋናው ይጻፋል እንጂ ሁሉ ሊጻፍ አይችልምና። ስለዚህ ሙሴ የጻፈው ቃል ትውፊትን አትቀበሉ አይልም። እንዲሁም እኔ ከጻፍኋቸው መጻሕፍት በቀር ሌሎች መጻሕፍትን (ነቢያትን፣ ዳዊትን፣ ወንጌልን፣ . . .) አትቀበሉ አይልም።

2) በራእየ ዮሐንስ 22፥18-19 ላይ ያለው ቃል ደግሞ የሚናገረው ስለ ራሱ ዮሐንስ ስለ ጻፈው የራእይ መጽሐፍ (ስለ ራእየ ዮሐንስ መጽሐፍ) እንጂ ስለ ሙሉው የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት አይደለም። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያሉት እያንዳንዳቸው መጻሕፍት "መጽሐፍ" ተብለው የሚጠሩ መሆኑ የታወቀ ነው። ለምሳሌ ትንቢተ ኢሳይያስን ሲያነብ የተገኘው ኢትዮጵያዊው ጃንደረባ "በሰረገላ ተቀምጦ የነቢዩን **የኢሳይያስን መጽሐፍ** ያነብ ነበር" ይላል። የሐዋ. 8፥28 ይህም ማለት የኢሳይያስ መጽሐፍ አንድ መጽሐፍ ነው ማለት ነው። እንዲሁም ቅዱስ ጴጥሮስ ይሁዳን በተመለከተ ከዳዊት መዝሙር ጠቅሶ ሲናገር "**በመዝሙር መጽሐፍ**፤ . . . ተብሎ ተጽፏልና" በማለት መዝሙረ ዳዊትን "መጽሐፍ" ብሎ ጠርቶታል። የሐዋ. 1፥20 ዮሐንስ ወንጌላዊም "ኢየሱስም **በዚህ መጽሐፍ** ያልተጻፈ ሌላ ብዙ ምልክት በደቀ መዛሙርቱ ፊት አደረገ" በማለት እርሱ የጻፈውን ወንጌል "መጽሐፍ" ብሎታል። ዮሐ. 20፥30

እንግዲህ እያንዳንዱ የመጽሐፍ ቅዱስ መጽሐፍ በራሱ "መጽሐፍ" እንደሚባል ግልጽ ነው ማለት ነው። ራሳቸው ፕሮቴስታንቶቹስ የሚቀበሉት መጽሐፍ ቅዱስ 66 መጻሕፍትን የያዘ አይደለምን? ስለሆነም ቅዱስ ዮሐንስ በራእዩ ላይ ". . .

*ማንም በዚህ በትንቢት መጽሐፍ ከተጻፉት ቃሎች አንዳች ቢያጎድል፣ በዚህ መጽሐፍ ከተጻፉት ከሕይወት ዛፍና ከቅድስቲቱ ከተማ እግዚአብሔር ዕድሉን ያጎድልበታል"* ያለው ያንኑ የራእዩን መጽሐፍ የተመለከተ ዐዋጅ እንጂ መጽሐፍ ቅዱስን በሙሉ የሚመለከት ዐዋጅ አይደለም። ስለዚህ ዮሐንስ ወንጌላዊ የራእይ መጽሐፉን በተመለከተ የጻፈውን የማስጠንቀቂያ ቃል ለሁሉም የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት እንደ ተነገረ አስመስሎ ማቅረብ ፈጽሞ የማይገናኝ ነገር ነው። ይህ ወይ አለማወቅ ነው፣ አለዚያ ደግሞ ሆን ብሎ ሰዎችን ለማሳሳት የሚደረግ ተንኮል ነው።

እንደዚሁም በራእየ ዮሐንስ ላይ ያለውን ይህን ቃል፣ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ይላል" የሚለው ሐሳባቸው፣ የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቀኖና ከታወቀና ካለቀ በኋላ ባለ አረዳድ ላይ ተመሥርቶ የሚቀርብ አረዳድና ትርጓሜ ነው። የራእየ ዮሐንስ መጽሐፍ የቀኖናዊነቱ ጉዳይ በጊዜያት ሂደት ሲወጣና ሲወርድ ነበር። ይህም ማለት ቀኖናዊነቱን በተመለከተ ወደ ኋላ ላይ የተነሡ ጥያቄዎችና ውዝግቦች ይነሡበት ነበር። በመላዋ ቤተ ክርስቲያን ዘንድ ቀኖናዊነቱ ወጥ ተቀባይነት ያገኘው ወደ አራተኛው መቶ ዓመት ማለቂያ ገደማ ነው።

ስለዚህ ይህ ፕሮቴስታንቶች የሚጠቅሱት ቃል እንኳንስ ሌሎቹን የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ቀኖና ለመወሰን መለኪያ ሆኖ ሊያገለግል ይቅርና ይህን ጥቅስ የያዘው መጽሐፍ ራሱ ቀኖናዊነቱ የተለያዩ ውጣ ውረዶችን አልፏል። ስለዚህ ራእየ ዮሐንስ በሐዲስ ኪዳን የመጻሕፍት ቀኖና ውስጥ ገብቶ፣ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ዝርዝርና ቁጥርም ተሰፍሮና ተቆጥሮ ካለቀ በኋላ፣ ቤተ ክርስቲያንም ራእየ ዮሐንስን ከሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት መጨረሻ ላይ እንዲቀመጥ ካደረገችው ዘንድ ይህን ተከትሎ የተገኘን አረዳድ ከጥንቱ የነበረ ዓይነት አስመስሎ ማቅረብ ከአለማወቅ የሚመጣ ነው። የራስን ሐሳብና አረዳድ በመጽሐፉ ቃል ላይ ለመጫን መሞከር ነው።

ፕሮቴስታንቶች ይህን አተረጓጎማቸውን ለማስጠበቅ ሲሉ እግዚአብሔር የመጻሕፍትን ቀኖና እና ራእየ ዮሐንስም የመጨረሻው የሐዲስ ኪዳን መጽሐፍ እንደሚሆን አስቀድሞ ስለሚያውቅ ነው፣ ስለዚህም የሐዲስ ኪዳንን ቀኖና በራእየ ዮሐንስ 22፥18-19 ባሉት ቃላት አተመው ይላሉ። ሆኖም ይህ አባባላቸው እውነት ከሆነ፣ ራእ. 22፥18-19 የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን ቀኖና የሚያትምና የሚዘጋ መሆኑን አንድ ክርስቲያን አስተማማኝ በሆነ መንገድ እንዴት ሊያውቅ ይችላል? ምክንያቱም ጥቅሱ በራሱ መጽሐፍ ይዘት ላይ የሚጨምርም ሆነ የሚቀንስ አይኑር ይላል እንጂ የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ብዛት 66 ስለሆነ ከ66 አትጨምሩ አትቀንሱ አይልምና። ስለዚህ

ይህ አባባላቸው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሯቸውን ያፈርስባቸዋል፤ ምክንያቱም ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ አረዳዳቸውን በጥቅሱ ላይ እየጫኑበት ነውና።

እንዲሁም የዚህን ጥቅስ ትርጓሜ እንዲህ ነው የሚሉት የመጻሕፍት ቀኖና በቤተ ክርስቲያን ተቀንኖ ያለቀ መሆኑን እነርሱ እውቅና ባይሰጡም ከቤተ ክርስቲያን ካገኙ በኋላ ነውና። ይህም ማለት አንድን ትንቢት ተፈጽሞ ካዩ በኋላ፣ ከመሆኑ አስቀድሞ በትንቢቱ የተነገረውን ነገር እኔም'ኮ አውቀው ነበር እንደ ማለት ያለ ነው።

ከዚህም ጋር ደግሞ ቅዱስ ዮሐንስ ራእዩን ሲጽፍ መጽሐፍ ቅዱስ ልክ እኛ አሁን በእጃችን ባለው መልኩ አንድ ላይ ተጠቃልሎና ተጠርዞ አልነበረም። ይህ የሆነው የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት በቀኖና ተለይተውና ተወስነው ከታወቁ ከብዙ ዘመናት በኋላ ነው። ከዚህም በተጨማሪ ሁሉም የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት እንዳሁኑ በቀላሉ አንድ ላይ ታተመው መገኘት የቻሉት የማተሚያ መሣሪያ ከተሠራበት ከ15ኛው መቶ ዓመት ወዲህ ነው። ስለዚህ ያን ጊዜ ቅዱስ ዮሐንስ "በዚህ መጽሐፍ" ሲል ራእዩን የጻፈበትን መጽሐፍ ማለቱ ነው እንጂ ከዚህ ውጭ መላውን መጽሐፍ ቅዱስ በሙሉ ነው ማለት ከታሪክም ከእውነታም የራቀ ፍጹም ፈጠራ ነው። ራሱ ቅዱስ ዮሐንስ **"ማንም በዚህ <u>በትንቢት መጽሐፍ</u> ከተጻፉት ቃሎች"** ብሎ በማያሻማ ሁኔታ ዐዋጁ የሚመለከተው ራእየ ዮሐንስን መሆኑን ግልጽ አድርጎ ነው የጻፈው። ስለዚህ ይህ የራእየ ዮሐንስ ዐዋጅ ክርስቲያኖች ከተጻፈው ውጭ ሌላ ምንም ነገር መመልከትም ሆነ መስማት የለባቸውም የሚል አይደለም። ፕሮቴስታንቶች የሚሉትና ጥቅሱ የሚለው ፍጹም የማይገናኙ ነገሮች ናቸው።

3. ሌላው ደጋግመው የሚጠቅሱት የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ይህ ነው፡-

> ነገር ግን ኢየሱስ እርሱ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደ ሆነ ታምኑ ዘንድ፣ አምናችሁም በስሙ ሕይወት ይሆንላችሁ ዘንድ <u>ይህ ተጽፏል</u>። ዮሐ. 20፡31

ሆኖም ይህ ቃል የሚገልጸው ወንጌላዊው መጽሐፉን ለምን እንደ ጻፈ እንጂ ከእርሱ ውጭ ሌላ አያስፈልግም የሚል አይደለም። አንድ መጽሐፍ ስለ ተጻፈበት ምክንያት ማስረዳት ማለት ያ መጽሐፍ ብቸኛና በቂ ነው፣ ከዚያ ውጭ ሌላ መጽሐፍም ሆነ ትምህርት አያስፈልግም ከማለት ጋር የሚገናኝ ነገር አይደለም። ስለሆነም ይህ ጥቅስ ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ ወንጌሉን የጻፈበት ዓላማ መጽሐፉን አንብበንና ተምረን በኢየሱስ ክርስቶስ አዳኝነት አምነን ሕይወትን እናገኝ ዘንድ መሆኑን ጻፈልን

እንጂ እኔ ከጻፍኩት በቀር ሌላ ነገር አያስፈልግም አላለም። እንኳን ወንጌላውያን ሐዋርያትን ይቅርና ማንንም ሰው ቢሆን ያላለውን ብሏል ብሎ መናገር ነውር ነው፤ ኃጢአትም ነው።

ሐዋርያው ቅዱስ ዮሐንስ በወንጌሉ ላይ እንደዚያ ያለው እነርሱ እንደሚሉት በወንጌሉ ላይ ከጻፈው ውጭ ሌላ ምንም ነገር አያስፈልግም ማለቱ ከሆነ፣ ከዚያ በኋላ ሦስት መልእክቶችን ለምን ጻፈ? በመልክቶቹ ላይ ለጻፈላቸው ሰዎችስ "እንድጽፍላችሁ የምፈልገው ብዙ ነገር ሳለኝ በወረቀትና በቀለም ልጽፈው አልወድም፤ ዳሩ ግን ደስታችሁ ፍጹም እንዲሆን ወደ እናንተ ልመጣ፤ አፍ ለአፍም ልናገራችሁ ተስፋ አደርጋለሁ" ለምን አለ? 2 ዮሐ. 12 እንደዛናም ሦስተኛውን መልእክቱን ለላከለት ጋይዮስ ለተባለው ሰው "ልጽፍልህ የምፈልገው ብዙ ነገር ነበረኝ፤ ዳሩ ግን በቀለምና በብርዕ ልጽፍልህ አልወድም፤ ነገር ግን ወዲያው ላይህ ተስፋ አደርጋለሁ፤ አፍ ለአፍም እንነጋገራለን" ለምን አለው? 2 ዮሐ. 13-14 ዮሐንስ ወንጌላዊን "በወንጌል ላይ ከጻፍኩት ውጭ ሌላ ነገር የለም አያስፈልግም" ብሏል ማለትኮ፣ ራሱ ቅዱስ ዮሐንስ በመልእክቱ ላይ እንደዚህ እያለ የተናገራቸውን ነገሮች በቀጥታ መቃወም ነው። መልእክታቱንም አያስፈልጉም እንደ ማለት ነው!

4. ሌላው ጥቅሳቸው ደግሞ ይህ ነው፡-

> ከምታነቡትና ከምታስተውሉት በቀር ሌላ አንጽፍላችሁምና፤ . . . 2 ቆሮ. 1፡13

ይህን ቃል ቅዱስ ጳውሎስ ከጻፍኩላችሁ በቀር ሌላ የለም ብሏል ለማለት አንዳንድ አለማወቃቸውን እንደ መሣሪያ የሚጠቀሙ ፕሮቴስታንቶች እንደ ማስረጃ ሊጠቀሙበት ይሞክራሉ። ሆኖም የቅዱስ ጳውሎስ ሐሳብ እነርሱ ከሚሉት ጨርሶ የማይገናኝ ነው። ቅዱስ ጳውሎስ እንደዚህ ያለበት ዋናው ምክንያት፣ ለቆሮንቶስ ክርስቲያኖች በላከላቸው በመጀመሪያው መልእክቱ ላይ ". . . በመቄዶንያም ሳልፍ ወደ እናንተ እመጣለሁ" ብሎ በአካል እንደሚጎበኛቸው ጽፎላቸው ነበር። 1 ቆሮ. 16፡5-6

ሆኖም ኋላ ላይ ግን ይህን ሐሳቡን ትቶ ወደ እነርሱ ሳይሄድ ሁለተኛውን መልእክቱን ላከላቸው። ያን ጊዜ ቢጽ ሐሳውያንና መሰል ክፉ ሰዎች ቅዱስ ጳውሎስ በቃሉ የሚናገረው እና በተግባር የሚያደርገው የተለያየ ነው እያሉ ማስወራት ጀመሩ። ስለዚህም ቅዱስ ጳውሎስ ይህን ያደረገው ምክንያት ስለነበረው እንጂ ቃሉና ተግባሩ የተለያየ ሰው በመሆኑ አለመሆኑን ለማስረዳት ሲል "ከምታነቡትና ከምታስተውሉት በቀር ሌላ አንጽፍላችሁምና" አለ። ከዚያም ይህን ይረዱለት ዘንድ "በከፊል ስለ እኛ እንዳስተዋላችሁ ፈጽማችሁ ታስተውሉት ዘንድ ተስፋ አደርጋለሁ" አለ። 2 ቆሮ. 1፡14

ከዚያም ባለፉ እመጣለሁ ብሎ መቅረቱን እንደ ትልቅ መግቢያ በመጠቀም ክፉ ሰዎች የጳውሎስ ትምህርቱም የማይታመን አይደለም፣ እውነትና ሐሰት የተቀላቀለበት ነው ብለው ማስወራት ጀመሩ። ይህ አለመሆኑን ሲገልጸም ብፁዕ ጳውሎስ እንዲህ አለ፡-

> እንግዲህ ይህን ሳስብ ያን ጊዜ ቀሊትን አሳየሁን? ወይስ በእኔ ዘንድ አዎን አዎን አይደለም አይደለም ማለት እንዲሆን ያን የማስበው በዓለማዊ ልማድ ነውን? . . . ለእናንተም የሚነገረው ቃላችን አዎንና አይደለም አይሆንም። በእኛ ማለት በእኔና በስልዋኖስ በጢሞቴዎስም በመካከላችሁ የተሰበከ የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ክርስቶስ አዎንና አይደለም አልነበረም፣ ነገር ግን በእርሱ አዎን ሆኖአል። . . . 2 ቆሮ. 1፡17-20

ማለትም ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ ያስተማርኋችሁ ትምህርት ሐሰት የሌለበት እውነት ብቻ ነው ማለቱ ነው። በመቀጠልም ይህን ያምኑ ዘንድ "በክርስቶስም ከእናንተ ጋር የሚያጸናንና የቀባን እግዚአብሔር ነው፣ ደግሞም ያተመን የመንፈሱንም መያዣ በልባችን የሰጠን እርሱ ነው" አላቸው። 2 ቆሮ. 1፡21-22 ከዚህ ሁሉ በኋላ በመጨረሻ ወደ እነርሱ ሊመጣ ብሏቸው የነበረውን ሐሳቡን የቀየረበትን መሠረታዊ ምክንያት እንዲህ ሲል ጻፈላቸው፡-

> እኔ ግን ልራራላችሁ ስል እንደ ገና ወደ ቆሮንቶስ እንዳልመጣሁ በነፍሴ ላይ እግዚአብሔርን ምስክር እጠራለሁ። . . . ደስ ሊያሰኙኝ ከሚገባቸውም በመምጣቴ ኀዘን እንዳይሆንብኝ ይህንኑ ጻፍሁላችሁ፣ . . . 2 ቆሮ. 1፡23 እና 2፡3

ስለዚህ ቅዱስ ጳውሎስ ያለው ትምህርቱና ድርጊቱ የተለያዩ አይደሉም፣ የማደርገው በጻፍኩላችሁ መልእክቶቼ እንደጻፍኩላችሁ እንጂ የምጽፍላችሁ ሌላ፣ በተግባር የማደርገው ደግሞ ሌላ አይደለም፣ ትምህርቴ የሚያጠራጥር ወይም ደግሞ አዎ እና አይደለም (እውነት እና ሐሰት) የተቀላቀለበት አይደለም ለማለት ነው እንጂ ከጻፍኩላችሁ ውጭ ሌላ የለም ከማለት ጋር ፈጽሞ የማይገናኝ ነገር ነው።

ፕሮቴስታንቶች የእምነታቸውና የአስተምህሯቸው መሠረትና ዋና ማዕከል ያደረጉትን ይህን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሯቸውን ከራሱ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በጣም ብዙ በሆኑ ጥቅሶች ማስረዳት እንደሚችሉ የሚያስብ ሰው ይኖር ይሆናል። ደግመው ደጋግመው ሁል ጊዜም የሚሉት ጉዳይ ከመሆኑ አንጻር እንደዚህ የሚያስብና የሚጠብቅ ሰው ቢኖር አይገርምም። ይህን እምነታቸውን የሚያረጋግጡ ብዙ ጥቅሶች ባይኖሩ እንኳ ቢያንስ የተወሰኑ ሁለትና ሦስት መሠረታዊ አስረጂ

የሆኑ ጥቅሶች እንዲኖሩ ግን ይገባ ነበር፣ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ "ሁሉ ነገር በሁለትና በሦስት ምስክር አፍ ይጸናል" ይላልና። 2 ቆሮ. 13:1 ሆኖም "ንጉሡ ራቁቱን ነው" ብሎ ተናገረ እንደሚባለው ሕፃን ልጅ፣ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚል አንድም ጥቅስ የለም። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ስለ ቅዱሳት መጻሕፍት በመንፈስ ቅዱስ መሪነት የተጻፉ መሆን፣ ስለ ጠቃሚነታቸው የሚናገሩ ብዙ ቦታዎች አሉ፤ ሆኖም ለክርስቲያኖች የሚያስፈልጋቸው መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ነው የሚል ግን አንድ ጥቅስ እንኳ የለም።

ስለዚህ እስካሁን በተለያዩ ነጥቦች እንደ ተመለከትነው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች መሠረታዊ መነሻና አስተምህሮ በራሱ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሌለ ነው። ስለዚህም ይህ አስተምህሯቸው በራሳቸው መመዘኛ መሠረት፣ ማለትም ሁሉም ነገር በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ተጽፎ መገኘት አለበት በሚለው አስተምህሯቸው መሠረት፣ ውድቅ ነው ማለት ነው። ራሳቸው ፈጥረው ራሳቸው ለሚጮኹለት ለዚህ የፈጠራ ትምህርት ምንጮቹ እነርሱ እንጂ መጽሐፍ ቅዱስ አይደለም። ስለዚህ ይህን አስተምህሮ ውድቅ የምናደርግበት ዋናው ምክንያት በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ እንደዚህ የሚል አንድም ጥቅስ የሌለ በመሆኑ ነው፣ ኢ.መጽሐፍ ቅዱሳዊ በመሆኑ ነው። በመጽሐፍ ቅዱስ የሌለ ብቻ ሳይሆን መጽሐፍ ቅዱስ በግልጽ የሚቃወመው የስህተት ትምህርት ነው። ጥብቅና እቆምላቸዋለሁ የሚላቸው መጻሕፍት ራሳቸው መልሰው ስህተቱን ይገልጡበታል፣ በእኛ ውስጥ እንደዚህ ያለ ትምህርት የለም ይሉበታል። ይህንም ወደፊት በቦታው ላይ እናየዋለን።

## 1.4 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን መመሪያ ራሳቸው ፕሮቴስታንቶቹ በተግባር ይከተሉታልን?

የፕሮቴስታንቶች የመጽሐፍ ቅዱስ አጠቃቀማቸው በተግባር ሲታይ ምን ይመስላል? እንደሚሉት መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ ከማንበብ ውጭ ሌላ ምንም ነገር አያደርጉምን? በስብሰባዎቻቸውስ መጽሐፍ ቅዱስን አንብበው ብቻ ነው የሚለያዩት? "መጽሐፍ ቅዱስን ማንበብ ብቻ በቂ ነው፣ ማንም ሰው ያለ አስተማሪና ተርጓሚ መረዳት ይችላል" እንደሚሉት የሚያምኑ ከሆኑ፣ አስተምህሮዎቻቸውን የሚያብራሩ መጻሕፍትን ለምን ይጽፋሉ? እነርሱ እንደሚሉት መጽሐፍ ቅዱስን ማንበብ ብቻ በራሱ የመጽሐፉን ሐሳብ ለመረዳት በቂ ከሆነ፣ ለምን መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ ማደል አይበቃቸውም? ሊያደርጉ የሚገባቸው መጽሐፍ ቅዱስን እያተሙ ማሰራጨት

ወይም ደግሞ የታተመውን እየገዙ ማደል ብቻ ነበር እንጂ ማስተማር፣ ማብራራት፣ ማገዝ፣ ማጥናት ከሚባሉ ነገሮች ውስጥ ከጫፋቸውም መድረስ አልነበረባቸውም! ምክንያቱም ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ሌላ ምንም ነገር አያስፈልግም ይላሉና።

ታዲያ የሚያስፈልገው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ከሆነ፣ የሚያዘጋጇቸው ብዙ የሆኑ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት መጻሕፍቶች፣ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት ሴሚናሮች፣ ስብከቶች፣ ሥልጠናዎች፣ . . . ለምን አስፈለጓቸው? በራሪ ወረቀቶችንና ሌሎች ማገገሚ መጣጥፎችንስ ለምን እያዘጋጁ ያሰራጫሉ? ለምንስ መጽሐፍ ቅዱስን ይሰብካሉ? ለምን መጽሐፍ ቅዱስን ለሕዝቡ አንብበው ብቻ ዝም አይሉም? መጽሐፍ ቅዱስን ቃል በቃል ከማንበብ ውጭ ያለ ማንኛውም ማብራሪያ "ትርጓሜ" እንጂ ራሱ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል አይደለምና።

ለአብነት ያህልም በፕሮቴስታንቶች ተጽፈው ከሚታተሙና ከሚሰራጩ ብዙ የመጽሐፍ ቅዱስ ማብራሪያ መጻሕፍቶቻቸው መካከል ጥቂቶቹ ብቻ ለማሳያ ከዚህ በታች ቀርበዋል።
























4

[4] God is Gay" የሚለው ይህ መጽሐፍ፣ ፕሮቴስታንቶች የመጽሐፍ ቅዱስ ማብራሪያ ብለው የጻፉት መጽሐፍ ነው። ዋና ይዘቱና ዓላማውም የግብረ ሰዶማዊነትን ኃጢአትነትና ርኩሰትነት በተመለከተ በግልጽ የተጻፉትን የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች ግብረ ሰዶማውይነትን በማይነቅፍ ሁኔታ ለውጦ ለማቅረብ የተደረገ ሙከራን የያዘ መጽሐፍ ነው። የመጽሐፉን ይዘት ከርእሱ ለመገመት ከባድ አይደለም።

ይህን የመሰሉ ስለ መጽሐፍ ቅዱስ እና ስለ እምነታቸው ለማስረዳት የተጻፉ በጣም ብዙ የሆኑ መጻሕፍት በየመጻሕፍት መደብሮቻቸውና ቸርቾቻቸው ሞልተዋል። ታዲያ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው እምነታቸውና ትምህርታቸው ከልባቸው የሚያምኑበት ከሆነ ይህን የመሰለው የመጽሐፍ ጋጋታ ለምን አስፈለገ?

ፕሮቴስታንቶች ይህን ሁሉ ተጨማሪ ጥረት የሚያደርጉት፣ ሰው መጽሐፍ ቅዱስን በማንበብ ብቻ ወደ አንድ ዓይነት አረዳድና አተረጓጎም እንደማይደርስ ስላወቁ አይደለምን? ስለዚህም እያንዳንዱ የፕሮቴስታንት ቡድን (ዲኖሚኔሽን) በእርሱ ሥር ያሉት ሰዎች ያን የእርሱን ዓይነት አተረጓጎምና አረዳድ (አስተምህሮና እምነት) ይይዙለት ዘንድ የራሱን የትርጓሜ፣ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት እና መሰል መጻሕፍትንና መጣጥፎችን ይጽፋል፣ ያስተምራሉ።

ያለ ማንም ርዳታና ማብራሪያ መጽሐፍ ቅዱስን ማንበብ ብቻውን ያ ቡድን (ዲኖሚኔሽን) የያዘውን እምነት እንዲያምኑና የዚያ ቡድን አተረጓጎም ላይ እንዲደርሱ የሚያደርግ ቢሆን ኖሮ መጽሐፍ ቅዱስን ማስተማር፣ ማስጠናት፣ . . . ለምን አስፈለጋቸው? ሌላው የፕሮቴስታንት ቡድንም እንደዚሁ በውስጡ ያሉትን ሰዎች መጽሐፍ ቅዱስን እርሱ በተረዳበት መንገድ ካላስተማራቸው ቃሉን በማንበብ ብቻ እርሱ ወደሚያራምደው ዓይነት አስተምህሮና እምነት እንደማይመጡ ስለሚያውቅ የራሱን አረዳድ በእነዚያ ሰዎች ላይ ለማስረጽ ይችል ዘንድ የመጽሐፍ ቅዱሱን ቃል በራሱ መንገድ ይተረጉምላቸዋል፣ ያስተምራቸዋል።

ስለ መጽሐፍ ቅዱስ አጠናን፣ እና ስለ ተለያዩ ነገረ ሃይማኖታዊ ጉዳዮች ብዙ መጻሕፍትንና ማስተማሪያ ነገሮችን የሚያዘጋጁት ለዚህ ነው። ስለዚህ **እነርሱም ይተረጒማሉ** ማለት ነው።

ታዲያ ይህ ተግባራቸው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን በቂ ነው" የሚለውን መሠረታዊ ትምህርታቸውን እንደሚቃወም አላስተዋሉትምን? በእርግጥ ፕሮቴስታንቲዝም የገባበትን የስህተት መንገድና ውጤቱን በሚገባ ተረድተው ከዚያ እየወጡና ወደ ሐዋርያዊቷ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን እየመጡ ያሉ ፓስተሮች፣ ግለሰቦች፣ ቤተሰቦች ብዙ ናቸው። ከዚያም በላይ የቴዎሎጂ ኮሌጅ ተማሪዎችና አስተማሪዎች ሳይቀሩ እንዳለ በቡድን ወደ ኦርቶዶክሳዊነት እየገቡ ያሉ አሉ። ከፕሮቴስታንት ወደ ኦርቶዶክሳዊ ክርስትና የተመለሰው ሊቀ ካህናት ጆሲያህ ትሬንሃም እንዲህ ይላል፡-

> ባለፉት 30 ዓመታት በዩናይትድ ስቴትስ አሜሪካ ውስጥ፣ ብዙ ሉተራውያን ምእመናን፣ እና ቁጥራቸው ቀላል የማይባል ካህናት ወደ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን መጥተዋል።"[5]

[5] Josiah Trenham, Rock and Sand, *An Orthodox Appraisal of the Protestant Reformers and Their Teachings*, p. 68.

እንድን መጽሐፍ ያነበበን ሰው "መጽሐፉ ምን ይላል?" ብለን ስንጠይቀው በዋናነት የምንፈልገው የመጽሐፉን ቃል ያንኑ መልሶ ቃል በቃል እንዲያነብልን ሳይሆን፣ ሐሳቡ ወይም ትርጉሙ ምን እንደሆነ እንዲነግረን ነው። ያን ጊዜ "የመጽሐፉ ሐሳብ እንደዚህ ነው" ብሎ የሚነግረን ሐሳብ፣ ያ ሰው ስለዚያ መጽሐፍ ያለው የራሱ አረዳድ (ትርጓሜ) ነው። የጠየቅነው ሰው የራሱን ትርጓሜ ካልነገረን ደግሞ ራሳችን ለራሳችን ለመተርጎም እንሞክራለን፣ ወይም ደግሞ የሌላን ሰው ትርጓሜ እንቀበላለን። መጽሐፍን ሳንተረጉም ለማንበብ አንችልም። ሆኖም ለምናነበው መጽሐፍ የምንሰጠው ትርጓሜ የራሱ የመጽሐፉ አካል ሳይሆን ከመጽሐፉ ውጭ ነው። ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስን ስናነብ ወይ ራሳችን በራሳችን መተርጎም አለብን (ይህ ደግሞ ስህተት ነው፣ 2 ጴጥ. 1፡20)፣ አለዚያ ደግሞ የሌላውን ሰው አረዳድ ወይም ትርጓሜ መቀበል ይኖርብናል።

ስለሆነም ፕሮቴስታንቶች ምንም እንኳ እውቅና ለመስጠት ባይፈልጉም፣ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን ለመረዳት የማይቻል እንደሆነ ያውቃሉ። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው በተግባር እንደማይሠራም ያውቃሉ። ስለሆነም እያንዳንዱ የፕሮቴስታንት አንጃ የየራሱ አተረጓጎምና አረዳድ አለው። መጥምቃውያን (ባፕቲስት) የተባሉት የፕሮቴስታንት ቡድኖች አንድ ዓይነት ነገሮችን የሚያምኑት፣ ሜቶዲስቶችም እንደዚሁ ከሌላው የፕሮቴስታንት አንጃ ተለይተው የራሳቸው የሆነ እምነት ያላቸው የሆኑት፣ ሌላው ብዙ ሺህ የሆነው የፕሮቴስታንት ቡድንም የየራሱ የሆነ ልዩ አስተምህሮና እምነት ያለው የሆነው፣ ሁሉም የየራሳቸው የሆነ አረዳድና አተረጓጎም ስላላቸው ነው እንጂ የእያንዳንዳቸው ቡድኖች አባላቶቻቸው መጽሐፍ ቅዱስን በግላቸው አንብበው የደረሱበት መደምደሚያ መጥምቃዊነት ወይም ሜቶዲስትነት ወይም የሌላው ቡድን ዓይነት እምነት ሆኖ አይደለም።

የተለያዩ የፕሮቴስታንት ቡድኖች አንድ ዓይነት መጽሐፍ ቅዱስን እያነበቡ አንድ ዓይነት እምነት የላቸውም፣ ለምን ቢባል ሁለቱም የሚያነቡትን መጽሐፍ ቅዱስ የሚረዱበት የየራሳቸው የሆነ አረዳድ ስላላቸው ነው። መጽሐፍ ቅዱስን የሚያነቡትና የሚረዱት የቡድናቸውን አስተምህሮና እምነት በሚደግፍና በሚያብራራ መንገድ ስለሆነ ነው።

እያንዳንዱን ቡድን በራሱ ተለይቶ እንዲታወቅና እንዲኖር ያደረገው የየራሱ የሆነ አረዳድና አተረጓጎም (ትውፊት) ስላለው ነው። ሆኖም ትውፊታቸው ከጌታ ያልተገኘ፣ ከሐዋርያት ጋር ትስስር የሌለው፣ ከቅርብ ዘመናት ወዲህ (ከእነ ሉተር፣ ካልቪን፣ ዝውንግሊና መሰሎቻቸው) የሚጀምር ስለሆነ፣ ግለሰብ ፓስተሮች በልካቸው የሚሠሩትና የሚያፈርሱት ስለሆነ፣ ስሜት መር ስለሆነ በአሸዋ ላይ እንደ ተሠራ

ቤት በቀሳሉ ይፈርሳል። "በእዚያ ቆዳ የተሠራ ቤት ይፈራርሳል ጅብ የሮጦ ሰበት" እንደሚባለው በሆነ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ወይም ሐሳብ ላይ የአረዳድ አለመግባባት ሲገጥማቸው ተጣልተው ይከፋፈሉና ወደ ሁለት ወይም ከዚያ በላይ ቡድኖች ይከፈላሉ። እነዚያም እንዲሁ በሆነ ጉዳይ እርስ በእርሳቸው ሲጣሉ ይከፋፈሉና ብዙዎች ይሆናሉ። እንዲህ እንዲህ እያሉ በ500 ዓመታት ውስጥ ከ40,000 እንኟ በልጦዋል። የፕሮቴስታንትን እንኟ በየጊዜው እየበዛ እንዲሄድ የሚያደርገው ይህ ዲሲፕሊን ነው። ከሆነ እንኟ ያሉ ሰዎች የዚያ ቡድን ትውፊት ደስ አላላቸው ሲል ከዚያ ይወጡና ሌላ ይመሠርታሉ፣ ከሌላውም ያሉት እንደዚሁ ሌላ ይመሠርታሉ። ሂደቱ አሁንም በአሳዛኝ ፍጥነት እንደ ቀጠለ ነው።

ስለሆነም ጥያቄው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው እንመን ወይስ ትውፊትንም እንጠቀም የሚለው አይደለም ማለት ነው። ምክንያቱም ፕሮቴስታንት ወገኖቻችንም እንዲሁ በአፋቸው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ በቂ ነው" ይበሉ እንጂ በተግባር ግን ይህን መርሕ የማይከተሉት መሆኑ ግልጽና የታወቀ ነውና።

ስለዚህ ጉዳዩ አንድ ሰው መጽሐፍ ቅዱስን በትክክል ለመረዳት ይችል ዘንድ የማንን አተረጓጎም ይከተል? የሚለው ነው። ከሐዋርያት ጀምሮ በቤተ ክርስቲያን የተጠበቀውንና እስከ ሰማዕትነት ድረስ በመሰከሩ ቅዱሳን አባቶች የተሰጠውን አተረጓጎም? ከቅዱሳን ሐዋርያት ጀምሮ በተነሡ ቅዱሳን አባቶች እየተብራራና እየተተረጎመ ሳይቋረጥ የመጣውን አረዳድ ወይስ ለ1,500 ዓመታት ያልነበረውንና ድንገት ብቅ ብሎ በራሱ መሠረትነት ተመሥርቶ "እኔ የተረዳሁት እንደዚህ ነው" የሚለውን ግለሰባዊ አረዳድ? ተአማኒነት ያለው የትኛው ትውፊት ነው? ሐዋርያዊ የሆነው ከሰማዕታትና ቅዱሳን አባቶቻችን አንሥቶ ለእኛ የደረሰው የኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ትውፊት? ወይስ ከተሐድሶ መሥራቾቹ ከእነ ሉተር በፊት መነሻ መሠረት ያልነበረውና በየጊዜው ማንኛውም ግለሰብ በራሱ መረዳትና ስሜት ልክ የሚፈጥረው ሰዋዊ "ትውፊት" ይሻላል? የሚለው ነው። ጉዳዩ ይኸ ነው!

## 1.5 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ኪሉች መሠረታዊ ችግሮቹ

1. **መጽሐፍ ቅዱስ ከተጻፈው ቃል ባሻገር ያልተጻፉ ሐዋርያዊ ትምህርቶችን (የቃል ትውፊትን) ልንቀበል እንደሚገባ ከሚናገረው ትምህርት ጋር ይቃረናል።**

ቅዱስ ጳውሎስ በመልእክቱ የጻፋቸውን ትምህርቶች ብቻ ሳይሆን በቃሉ ያስተማራቸውን ትምህርቶችም መጠበቅ እንደሚገባ በመልእክቶቹ ደጋግሞ አሳስቧል። ለምሳሌም በ2ኛ የተሰሎንቄ መልእክቱ ላይ እንዲህ ብሏል:-

> እንግዲያስ፣ ወንድሞች ሆይ፣ ጸንታችሁ ቁሙ፣ **<u>በቃላችንም</u>** ቢሆን ወይም በመልእክታችን **<u>የተማራችሁትን ወግ ያዙ</u>**። 2 ተሰ. 2፡15

"በመልእክታችን የተማራችሁትን" ያለው በመልእክቶቹ የጻፈላቸውን መሆኑ ግልጽ ሲሆን፣ "**<u>በቃላችን የተማራችሁትን ወግ (ትውፊት) ያዙ</u>**" ያለው ደግሞ በመልእክቶቹ ያልተጻፉ ተግባራዊና ሕይወታዊ ትምህርቶቹን እንዲይዙ (እንዲጠብቁ) ማሳሰቡ መሆኑ ግልጽ ነው። ይህ የቅዱስ ጳውሎስ መልእክት ቢያንስ **<u>ሦስት</u>** መሠረታዊ ነገሮችን ያስረዳናል፤ እነዚህም፡-

1) በሐዋርያዊው በቅዱስ ጳውሎስ ትምህርት ውስጥ ሕያው የሆኑ ትውፊቶች የነበሩ መሆናቸውን፣

2) ክርስቲያኖች በእምነት የተመሠረቱት እነዚህን ትውፊቶችም በመያዛቸው መሆኑን፣ እና

3) እነዚህ ትውፊቶች ሁለቱም ዓይነት - የተጻፉ እና ያልተጻፉ - መሆናቸውን በግልጽ ያስረዳል።

እንግዲህ መጽሐፍ ቅዱስ ራሱ በግልጽ ቋንቋ የቃል (ያልተጻፉ) ትውፊቶች ተአማንያን መሆናቸውን፣ እና ምንጫቸውም ሐዋርያዊ መሆኑን፣ እንደዚሁም የእምነት አካል ተደርገው ሊጠበቁ የሚገባቸው መሆናቸውን እየመሰከረ፣ ፕሮቴስታንቶች አንቀበላቸውም የሚሉት በምን ምክንያት ነው?

በተለይም እዚህ ላይ "**<u>በቃላችንም</u>** ቢሆን ወይም በመልእክታችን **የተማራችሁትን ወግ <u>ያዙ</u>**" በሚለው ትእዛዝ ውስጥ **"<u>ያዙ</u>"** የሚለው ቃል በግሪኩ ክራቴይት - Κρατεῖτε - የሚለው ግሥ ሲሆን፣ እርሱም "አንድን ነገር በኃይል አጽንቶ መያዝ፣ ማጥበቅ" ማለት ነው።[6] ሙሉ ቃሉ እንዲህ ነው፡- "Κρατεῖτε τάς παραδόσεις - hold fast the Traditions – **የተማራችሁትን ትውፊት (ወግ) [አጽንታችሁ] ያዙ።**" ስለዚህ ሐዋርያው ቅዱስ ጳውሎስ ከእርሱ በትውፊት ያገኙትን ትምህርት አጥብቀው እንዲይዙ መከራቸው እንጂ ከተጻፈው ውጭ ያለን የቃል ትውፊት ንቆና አቃልሎ አላስተማራቸውም። እንዲህ ያለው ነገር ከቅዱሳን ሐዋርያት አስተምህሮ የራቀ ነው።

ቅዱስ ዮሐንስ አፈ ወርቅ ይህን የቅዱስ ጳውሎስ መልእክት ሲተረጉም እንዲህ ብሏል፡-

> ስለዚህም ሐዋርያት ሁሉንም ነገር በመልእክቶቻቸው ጽፈው የሰጡን አለመሆናቸው ግልጽ ነው፣ ነገር ግን ብዙ ነገሮችን ሳይጽፉ በቃል አስተላለፉልን እንጂ። እነዚህ ሁለቱም፣ የተጻፉትም ሆነ ሳይጻፉ በቃል ከእነርሱ የተላለፉልን ሊታመኑ የሚገባቸው ናቸው። ስለዚህም

[6] W. E. Vine [Protestant Author], *Vine's Expository Dictionary of New Testament Words*, p. 387.

የቤተ ክርስቲያን ትውፊት ዋጋ ያለውና ሊታመን የሚገባው መሆኑን እንገንዘብ። ትውፊት ነው፤ ከዚህ ወዲያ አትሻ።[7] (ትርጓሜ መልእክተ ተሰሎንቄ ካልእ፣ ክፍለ ትምህርት 8)

ለጢሞቴዎስ በላከለት በሁለተኛው መልእክቱ ላይም "... ከእኔ የሰማኸውን ጤናማ ቃል ምሳሌ ያዝ" በማለት የጻፈለትን ቃል ብቻ ሳይሆን የሰማውንም መያዝ እንዳለበት ነግሮታል። 2 ጢሞ. 1፥13

እንደዚሁም "አንተ ግን ትምህርቴንና አካሄዴን፣ አሳቤንም፣ እምነቴንም፣ ትዕግሥቴንም፣ ፍቅሬንም፣ መጽናቴንም፣ ስደቴንም፣ መከራዬንም ተከተልህ" (ቁ. 10) ካለው በኋላ ይቀጥልና "አንተ ግን በተማርህበትና በተረዳህበት ነገር ጸንተህ ኑር፣ ከማን እንደ ተማርኸው ታውቃለህና" (ቁ. 14) አለው። ጢሞቴዎስ ከአባቱ ከቅዱስ ጳውሎስ የተማረባቸውና የተረዳባቸው ነገሮች በጽሑፍ ጽፎ የላከለት ብቻ ሳይሆን በቃሉና በሕይወቱ ያስተማረው ሁሉ ነው። "ትምህርቴንና አካሄዴን፣ አሳቤንም፣ እምነቴንም፣ ትዕግሥቴንም፣ ፍቅሬንም፣ መጽናቴንም፣ ስደቴንም፣ መከራዬንም ተከተልህ" ያለው ለዚህ ነው። "በመልእክቴ ብቻ ተማርህ" አላለውም!

ቅዱስ ጳውሎስ እንደገናም በ1ኛ ቆሮንቶስ 11፡2 ላይ "ወንድሞች ሆይ፣ በሁሉ ስለምታስቡኝና አሳልፌ እንደ ሰጠኋችሁ ወግን (ትውፊትን) ፈጽማችሁ ስለ ያዛችሁ አመሰግናችኋለሁ" ይላል። "አሳልፌ እንደ ሰጠኋችሁ ወግን" ማለት በጽሑፍ ያልተጻፈ፣ በቃልና በተግባር በሕይወት ያስተማራቸውን በሙሉ ማለት ነው። የቆሮንቶስ ክርስቲያኖች ይህን በማድረጋቸው (ትውፊትን በመጠበቃቸው) "አመሰግናችኋለሁ" አላቸው እንጂ "እንዴት እንደዚህ ታደርጋላችሁ?" ብሎ አልወቀሳቸውም፤ በመልእክቴ ከጻፍኩላችሁ በስተቀር ለምን ሌላ ነገር ጠበቃችሁ? አላላቸውም።

ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ፣ ቅዱሳን አባቶቻችን ሐዋርያት በቃላቸውና በሕይወታቸው ያስተማሩትን ትምህርት እንቀበልና እንጠብቅ ዘንድ፣ ለሌሎችም እናስተምር ዘንድ በግልጽ ከሚናገረው ከመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት ጋር በቀጥታ የሚቃረን ጸረ መጽሐፍ ቅዱስ አስተምህሮ ነው።

## 2. ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን አስገኘች እንጂ መጽሐፍ ቅዱስ ቤተ ክርስቲያንን አላስገኘም።

### 1) ቤተ ክርስቲያን ከመጽሐፍ ቅዱስ በፊት የነበረች ናት። የክርስትና ሃይማኖት በመጽሐፍ ላይ ብቻ የተንጠለጠለ ሃይማኖት አይደለም።

[7] (Hence it is manifest, that they did not deliver all things by Epistle, but many things also unwritten, and in like manner both the one and the other are worthy of credit. Therefore let us think the tradition of the Church also worthy of credit. It is a tradition, seek no farther.)

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ ቤተ ክርስቲያን ከመጽሐፍ ቅዱስ በፊት የነበረች መሆኗን ያልተረዳ አስተምህሮ ነው። የክርስትና ሃይማኖት የ "እግዚአብሔር ቃል ሃይማኖት" ነው። ይህ ቃልም በወረቀት ላይ በተጻፈው ብቻ የተገደበ ሳይሆን በቃልና በሕይወት በቤተ ክርስቲያን ውስጥ የነበረው ሥርዐተ አምልኮውና መርሐ እምነቱ ሁሉ ነው። መጻሕፍቱን በእግዚአብሔር መንፈስ የጻፏቸው በብሉይ ኪዳን ዘመን የብሉይ ኪዳን የቤተ ክርስቲያን (የእግዚአብሔር ሕዝብ) አካል የሆኑት እስራኤላውያን፤ በሐዲስ ኪዳን ደግሞ የሐዲስ ኪዳን የቤተ ክርስቲያን አካላት ናቸው። ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ልጆቿ ከእርሷ መጽሐፍ ቅዱስን እንዲያነቡና እንዲማሩ ትመክራለች።

ጌታችንና አምላካችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ደቀ መዛሙርቱን "ወደ ዓለም ሁሉ ሂዱ፤ ወንጌልንም ለፍጥረት ሁሉ ስበኩ" አላቸው እንጂ "መጽሐፍ ጻፉ" አላላቸውም። ማር. 16፥15 እንዲሁም "ከዚህም በኋላ ኢየሱስ ራሱ ለዘላለም ድኅነት የሆነውን የማይለወጠውን ቅዱስ ወንጌል . . . በእጃቸው ላከው" ሲል ቃሉን ማለቱ ነው እንጂ በብራናና በወረቀት ላይ የተጻፈ መጽሐፍ ማለት አይደለም። ማር. 16፥8 ስለዚህም ሐዋርያት ወንጌልን ለመስበክ ወደ ዓለም ሁሉ የተሰማሩት የሚያስተምሩበት መጽሐፍ ጽፈው ከዚያ ላይ ምዕራፍና ቁጥር እየጠቀሱ አልነበረም።

እንግዲህ እነዚህ ሁሉ የሚያስረዱን ጌታችን ሐዋርያቱን በስሜ መጽሐፍ እየጻፋችሁ ዓለምን ሁሉ ስበኩ ብሎ ሲያዝዛቸው የማናገኝ መሆኑን ነው። ትኩረቱ ወንጌልን መስበክ ላይ እንጂ የግድ በመጻፍ፤ በማተምና በማሰራጨት ላይ አልነበረም። ጌታችን በደሙ የመሠረተው ቤተ ክርስቲያንን ነው፤ የመዳን ጸጋ የሚገኝባቸው ምስጢራት የሚፈጸሙትም በዚች በሥጋው መቆረስ በደሙ መፍሰስ በመሠረታት ቤተ ክርስቲያን ነው። መጻሕፍቱ ሳይጻፉም ትምህርቱና ሕይወቱ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ይተገበርና ይፈጸም ነበር። መጻሕፍቱ ሳይጻፉ ቤተ ክርስቲያን ነበረችና።

ጌታችን ከሁሉ በፊት የመሠረተውና የሰጠው ቤተ ክርስቲያንን ነው እንጂ መጽሐፍን አይደለም። በሥጋዌው በጀመረውና በሥጋው መቆረስና በደሙ መፍሰስ በፈጸመው የማዳኑ ጸጋ ሕያዊት የሆነች ቤተ ክርስቲያንን ለራሱ ዋጀ። "በገዛ ደሙ የዋጃትን የእግዚአብሐርን ቤተ ክርስቲያን" ተብሎ እንደ ተጻፈ። የሐዋ. 20፥28 ጌታችን ደቀ መዛሙርቱን ሲያስተምራቸው የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን በቃሉ አላስጻፋቸውም፤ ሲያርግም መጽሐፍን አልሰጣቸውም፤ ወደ ዓለም ሲልካቸውም ወንጌልን ስበኩ አላቸው እንጂ የተጻፈ መጽሐፍ በእጃቸው አልሰጣቸውም። "ወንጌል" ማለት "የምሥራች፤ መልካም ዜና" ማለት ነው እንጂ የግድ የተጻፈ ብቻ ማለት አይደለምና። ለዚህ ነው ቅዱስ ጳውሎስ የአካላዊ ቃልን ሰው ሆኖ የመገለጥና ሰውን የማዳን ነገር ገና

ከመሆኑ ከ2000 ዓመታት አስቀድሞ ለአብርሃም መንገሩን ሲገልጽ "በአንተ አሕዛብ ሁሉ ይባረካሉ ብሎ ወንጌልን ለአብርሃም አስቀድሞ ሰበከ" ያለው። ገላ. 3፥8 እንዲሁም ከአራቱ ወንጌሎች እንዳቸውም ከመጻፋቸው በፊት ወንጌልን መስበኩን ሲናገር "በመጀመሪያ ወንጌልን በሰበክሁላችሁ ጊዜ . . ." ብሏል። ገላ. 4፥13

የመጀመሪያዎቹ ክርስቲያኖች ጌታችን ከሙታን መነሣቱን ያመኑት የዓይን ምስክሮች የሆኑት ቅዱሳን ሐዋርያት ስላስተማሯቸውና ያ ትምህርትም በቅብብሎሽ ይተላለፍና ይደርስ ስለነበር ነው እንጂ የሉቃስ ወንጌል ወይም የማቴዎስ ወንጌል ተብሎ ተጠቅሶ ስለ ተነገራቸው አልነበረም። 1 ቆሮ. 15፥1-8፤ 2 ጴጥ. 1፥16 ፤ የሐዋ፣ 2፥42 ፤ 1 ቆሮ. 11፥2 ፤ 1 ተሰ. 2፥13፤ 2 ተሰ. 2፥15 ፤ 3፥6 ስለዚህ ቤተ ክርስቲያን የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን አስገኘቻቸው እንጂ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ቤተ ክርስቲያንን አላስገኟትም። ቤተ ክርስቲያን የተመሠረተችው በቅዱስ ሥጋው መቆረስና በክቡር ደሙ መፍሰስ በዕለተ ዓርብ ነው እንጂ መጻሕፍቱ ሲጻፉ ወይም ከተጻፉ በኋላ አይደለም።

መጻሕፍቱ ከቤተ ክርስቲያን ከትምህርቷና ከሕይወቷ ሊጻፍ የሚችለውንና የሚገባውንም ያህል የሚገልጡ ብቻ ናቸው። ከዚያ ባሻገር ግን የምስጢራቱ ተግባራዊ አፈጻጸም፣ ረቂቃዊ ሕይወቷ፣ . . . ሁሉም ሊጻፉ አይችሉም። ለምሳሌም ቅዱስ ጳውሎስ ምስጢረ ቁርባንን በተመለከተ ለቆሮንቶስ ክርስቲያኖች በመልእክቱ ላይ ማለት የሚቻለውን ያህል ካለ በኋላ "የቀረውንም ነገር በመጣሁ ጊዜ እደነግጋለሁ" ያለው ለዚህ ነው። 1 ቆሮ. 11፥34 ስለዚህ ወንጌላውያን የቤተ ክርስቲያንን ትምህርቷን ሊጻፍ በሚቻለው ደረጃ ጻፉ እንጂ መጻሕፍቱ የተዘጋጁት ቤተ ክርስቲያንን ሙሉ በሙሉ ሊተኩ አይደለም።

መንፈስ ቅዱስ ለሐዋርያት ሲሰጥና በአንድ ቀን ስብከት 3,000 ሰዎች አምነው ሲጠመቁ አንድ እንኳ የተጻፈ የሐዲስ ኪዳን መጽሐፍ ገና አልነበረም። ሆኖም ቅድስት ቤተ ክርስቲያን 3,000 ልጆችን አገኘች። በመቀጠልም ሌሎች 5,000 ነፍሳት ተጨመሩላት፣ እንዲህ እያለች ሰዎች የእግዚአብሔርን ጸጋ እንዲያገኙ የማድረግ ተግባሯን እየከወነች ነበር። ሆኖም እስከዚያ ድረስ የተጻፈ አንድም እንኳ የሐዲስ ኪዳን መጽሐፍ አልነበረም። ቤተ ክርስቲያን ህልውናዋና ተግባሯ በመጽሐፍ ላይ የተንጠለጠለና "መጽሐፍ ላይ ብቻ" የተመሠረተ ቢሆን ኖሮ፣ ከጌታችን ዕርገት ከብዙ ዓመታት በኋላ ቢያንስ የመጀመሪያው ወንጌል እስከሚጻፍ ድረስ እንኳ አንድም ሥራ ባልሠራች ነበር። ነገር ግን እንደዚያ አይደለችም።

ሁሉም የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ገና ተጽፈው እንኳ ሳያልቁ በክርስቶስ ራስነትና በመንፈስ ቅዱስ ኃይል ላይ እንጂ በመጽሐፍ ላይ የተመሠረተች ያይደለችው ቅድስት ቤተ ክርስቲያን መልካሙን ዜና በዚያን ዘመን መልክዐ ምድራዊ መረዳት "ጽንፈ ዓለም" ተብሎ ይጠራ እስከ ነበረው እስከ እልዋሪቆን ድረስ ሰብካ ነበር። "ስለዚህ ከኢየሩሳሌም ጀምሬ እስከ **እልዋሪቆን** ድረስ እየዞርሁ የክርስቶስን ወንጌል ፈጽሜ ሰብኬያለሁ" እንዳለ ታላቁ ሐዋርያ ቅዱስ ጳውሎስ። ሮሜ 15፡19 እንደዚሁም አይነኬ ይመስል ከነበረው ከቄሣር ቤተ መንግሥት ውስጥም ደርሳ ነበር። ፊል. 4፡22

መጽሐፍ ቅዱስ የክርስትና እምነት መሠረቱ ወንጌልን መስበክ መሆኑን በስፋት ይናገራል። 1 ጴጥ. 1፡13፣ 2፡2፣ 1፡25 ፤ ሮሜ 10፡17፣ 1 ቆሮ. 15፡1-2 ፤ ማር. 16፡15 እነዚህ ሁሉ የሚያስረዱን ክርስትና መጀመሪያ ሲሰበክ የነበረው በቃል የነበረ መሆኑን ነው። ይህም በቤተ ክርስቲያን ይሰጥ የነበረ የቃል ስብከት ሲሆን ሐዋርያዊ ትውፊት ሆኖ ይተላለፍ ነበር። በኋላም ከዚያ ስብከት መካከል የተወሰነው በመጽሐፍ ተጻፈና የመጽሐፍ ቅዱስ አካል ሆነ። ሆኖም የክርስትና እምነት ዋናው ማዕከሉ የማያልፈው የእግዚአብሔር ቃል (ማር. 13፡31) እንጂ "የተጻፈ መጽሐፍ ብቻ" ሆኖ ግን አያውቅም።

ስለሆነም ወንጌል ማለት የክርስቶስ ሰው መሆንና ከዚህ የተነሣ የሰው ልጅ ያገኘውን በጸጋ ላይ ጸጋ ሰው ሁሉ ተረድቶ እንዲጠቀም ማስተማር እንደመሆኑ፣ ይህን የምሥራች ሐዋርያት ወደየተሰማሩበት እየሄዱ አስተማሩ እንጂ በዚያን ጊዜ "የማቴዎስ ወንጌል"፣ "የማርቆስ ወንጌል"፣ "የሉቃስ ወንጌል"፣ "የዮሐንስ ወንጌል" አልነበሩም። የተጻፈ የሐዲስ ኪዳን መጽሐፍ ያልነበረ መሆኑ ግን ቅድስት ቤተ ክርስቲያንን ተልእኮዋን ከመፈጸም አላዘገያትም፣ አላገዳትምም።

ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ህልውናዋ በመጽሐፍ ላይ ብቻ የተመሠረተ (የመጽሐፍ ጥገኛ) ቢሆን ኖሮ፣ መጀመሪያ መጻሕፍቱ እስከሚጻፉ ድረስ፣ ቀጥሎ ደግሞ በዘመኑ ከነበሩት አስመሳዮች ከሆኑ የግኖስቲኮች የፈጠራ መጻሕፍት ተለይተው እስከሚታወቁና እስከሚሰባሰቡ ድረስ አንዳችም የማዳን ተልእኮዋን መሥራት ባልጀመረች ነበር። ይልቁንም የመጀመሪያ ሥራዋ የምታደርገው መጽሐፍ መጻፍና መሰብሰብ በሆነ ነበር። ግን እንዲህ ስላልሆነች እንደዚያ አላደረገችም። እንደዚሁም ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ህልውናዋ በመጽሐፍ ላይ የተንጠለጠለ ሆኖ ቢሆን ኖሮ፣ መጻሕፍቶቿን በእሳት በማቃጠል የሚያጠፏት መስሏቸው የነበሩ የተለያዩ ክፉ ነገሥታትና ባለሥልጣናት በተሳካላቸው ነበር። ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ግን መጻሕፍቶቿ ሲቃጠሉባት ብታዝንም መጻሕፍቶቿን ያቃጠሉት ተንዱ እንጂ እርሷ ግን ዘመናትንና አዝማናትን ተሻግራ ይኸው አለች!

በቅርብ ዘመን እንኳ እንደ መሰከረም ሙሿ ግንኖና ሰፍኖ አይነኬ መስሎ በነበረው የማርክሲዝም ሌኒኒዝም ዳርዊናዊ ቁስ አካላዊነት ተወርረው በነበሩት አገራት መጽሐፍ ቅዱስ እንዳይሰበክ በመከልከል ቤተ ክርስቲያን የምትጠፋ መስሏቸው ብዙ ታግለዋታል። ዛሬም ቢሆን በዚህ ዙሪያ እየተሠሩ ያሉ ብዙ ነገሮች መኖራቸው የታወቀ ነው። ሆኖም ጌታ የመሠረታት ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ሙሽራዋ ክርስቶስ የሚደለዩት ስለሆነ መጻሕፍቶቿን በምንም መንገድ ይሁን በምን እናጠፋለን በማለት እርሷን ማጥፋት አይቻልም፤ እርሷ የመጻሕፍት ጥገኛ አይደለችምና! "የእውነት ዐምድ እና መሠረት" እንደ መሆኗ፤ እውነት የሆነው የእግዚአብሔር ቃል ያለው በውስጧ ስለሆነ መጻሕፍቱ ያን እውነት ጽፋ የምትገልጥባቸው አንድ መንገድ ናቸው እንጂ ብቸኛዎቹና ከዚያ ውጭ ምንም መንገድ የሌላት አይደለችምና። 1 ጢሞ.3፥15 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ግን ይኸን የቤተ ክርስቲያን ምንነት የዘነጋ ነው። መጻሕፍቱ ራሳቸው የተጻፉት በቤተ ክርስቲያን በሚፈጸሙት እና መንፈስ ቅዱስ በሚከውናቸው አምላካዊ የመዳን ጸጋ በሚገኝባቸው ምስጢራት እንድንጠቀም እንዲመሩን እንጂ በዚያው እንድንቀር አይደለም።

**2) የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቀኖና የተወሰነው በቤተ ክርስቲያን ነው።**

**ቅዱሳት መጻሕፍት የተጻፉት በቤተ ክርስቲያን እንደሆነው ሁሉ፣ የተመረጡትና የተሰባሰቡትም እንዲሁ በቤተ ክርስቲያን ነው።**

ይህ ምን ማለት እንደሆነ በሚገባ ለመረዳት፣ መጽሐፍ ቅዱስ በአንድ ላይ ተሰባስቦና ተጠርዞ እኛ ባለንበት ዘመን በእጃችን ላይ እንደምናገኘው ባለ ሁኔታ ያልነበረባቸውን በተለይ የመጀመሪያዎቹን ሦስትና አራት መቶ ዓመታትን መረዳትና ማሰብ የግድ ይላል። "መጽሐፍ ቅዱስ" በሚለው መድበል ውስጥ የሚገቡት መጻሕፍት የትኞቹ ናቸው? ስንት ናቸው? . . . የሚለው ጥያቄ በአንድ ቀን ያለቀ ጉዳይ አልነበረም። ብዙ ዘመናትን ወስዷል፣ የብዙ ታላላቅ አባቶችን ጥረትና ድካም፣ የተለያዩ ጉባኤያትን ውሳኔዎች ጠይቋል። እኛ በእነርሱ ድካም ስለ ገባን ያ ሂደትና ውጣ ውረድ ምናልባት ለብዙዎቻችን ላይታየን ይችል ይሆናል። ሆኖም መጽሐፍ ቅዱስ ራሱ በራሱ "በውስጤ ያሉት መጻሕፍት እነዚህ ናቸው፣ ቁጥራቸውም ይህን ያህል ነው" የሚል ዐዋጅ ያለው መጽሐፍ አይደለም። መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ አላሰባሰበም፤ በቤተ ክርስቲያን ተሰባሰበና ተቀነነ እንጂ።

ግኖስቲኮች የተባሉት መናፍቃን በ1ኛውና በ2ኛው መቶ ዓመት የራሳቸውን የፈጠራ ትምህርት እየጻፉ ከቅዱሳን ሐዋርያት መካከል የአንዱን ስም እየሰጡ ብዙ መጻሕፍትን ያሰራጩ ነበር። ከዚህ የተነሣም ጌታችን ለሐዋርያት ያስተማረውንና የሰጠውን፤ ሐዋርያትም የሚያስተምሩትን ትምህርት የያዙትን እውነተኛዎቹን መጻሕፍት

ከመናፍቃኑ የሐሰት መጻሕፍት ለይቶ ለማወቅ ፈተናነቱ ቀላል አልነበረም።

ከእውነተኞቹ ወንጌሎች ጋር አብረው ተቀላቅለውና ተመሳስለው ይሠራጩ ከነበሩት የግኖስቲኮች መጻሕፍት መካከል ዋና ዋናዎቹ የሚከተሉት ነበሩ[8]፣

| | | | |
|---|---|---|---|
| 1. | የቶማስ ወንጌል | 14. | የሉቃስ ወንጌል |
| 2. | የእንድርያስ ወንጌል | 15. | የናዝራውያን ወንጌል |
| 3. | የፊልጶስ ወንጌል | 16. | የኢቢዮናውያን ወንጌል |
| 4. | የማርቆስ ወንጌል | 17. | የሂራቅሊዮን ወንጌል |
| 5. | የማትያስ ወንጌል | 18. | የአሥራ ሁለቱ ወንጌል |
| 6. | የዕብራውያን ወንጌል | 19. | የያዕቆብ ወንጌል |
| 7. | የመርቅያን ወንጌል | 20. | የጴጥሮስ ወንጌል |
| 8. | የማቴዎስ ወንጌል | 21. | የመድኃኔ ዓለም ወንጌል |
| 9. | የባሲሊዲስ ወንጌል | 22. | የዮሐንስ ወንጌል |
| 10. | የእውነት ወንጌል | 23. | የያዕቆብ ምስጢራዊ መጽሐፍ |
| 11. | የማርያም ወንጌል | 24. | የኤጲፋንዮስ ወንጌል |
| 12. | የአራቱ ሰማያውያን ኃይላት ወንጌል | 25. | የበጥሊሞስ ወንጌል |
| 13. | የይሁዳ ወንጌል | 26. | . . . |

ከእነዚህ ውስጥ ከአራቱ በስተቀር ሌሎቹ የመናፍቃን መጻሕፍት ነበሩ። ታዲያ ከዚያ ሁሉ የመናፍቃን መጻሕፍት ገለባ መካከል አራቱን ስንዴ ወንጌሎች ማን ለይቶ አወጣቸው? እንዴትስ እነዚያ ብቻ (ማለትም አራት ብቻ) መሆናቸው ታወቀ?

ዛሬ ያለን ሰዎች ወንጌል ሲባል እንደምንረዳው የታወቁትን አራቱን ወንጌሎች ማለት ባልነበረባቸው በእነዚያ ዘመናት ክርስቲያኖች ስለ ክርስትና ሕይወትና ትምህርት ግራ ተጋብተው ነበረን? በጭራሽ! ለምን? ቢባል ጌታችን ያስተማረው የሕይወት ትምህርት እና ያ ሕይወት የሚሰጥባቸው ምሥጢራት በቤተ ክርስቲያን ከበዓለ ሃምሳ ጀምሮ በመንፈስ ቅዱስ እየተፈጸሙ በተግባር እየተኖሩ ስለነበር ነው። ከጌታ የተገኘውን ትምህርትና ሕይወት ተቀብለው በሚያቀብሉ አባቶች መስመር በነበረችው ቤተ ክርስቲያን ውስጥ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ተጽፈው ያላቁ የነበሩ መሆናቸው፤ ወይም ደግሞ በሐዋርያት ስም ይሠራጩ የነበሩ ብዙ የፈጠራ መጻሕፍት የነበሩ መሆናቸው ክርስቶስ ለቤተ ክርስቲያን የሰጣትን እውነተኛውን

[8] Elaine Pagels, *The Gnostic Gospels*, 1979.

ሕይወትና ትምህርት ለመለየት ብዙም አላስቸገራቸውም። ምክንያቱም እነርሱ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ስለነበሩ እውነቱን ያውቁትና ይኖሩት ነበርና። ይህም የአንድ ቤተሰብ አባል የሆነ ወይም ከቤተሰቡ ጋር አብሮ የኖረ ሰው፣ ከቤተሰቡ መካከል እንግዳ ቢቀላቀል በቀላሉ ለመለየት እንደማይቸገረው ማለት ነው።

በአንጻሩ ግን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚሉ ሰዎች በዚያ ዘመን አልነበሩም እንጂ ኖረው ቢሆን ኖሮ መጀመሪያ የሚቀርብላቸው ጥያቄ "ከእነዚህና ከመሰል የግኖስቲኮች መጻሕፍት መካከል እውነተኞቹን ወንጌሎች ማን ለይቶ አስቀመጣቸው?" የሚል ነው።

"የማቴዎስ ወንጌል" ማቴዎስ የጻፈው ስለመሆኑ አንድም ቦታ ላይ አይናገርም። ቅዱስ ማቴዎስ ወንጌሉን መጻፍ የጀመረው "የዳዊት ልጅ የአብርሃም ልጅ የኢየሱስ ክርስቶስ ትውልድ መጽሐፍ። አብርሃም ይስሐቅን ወለደ፤ . . ." ብሎ ነው እንጂ "ይህ ወንጌል ከአሥራ ሁለቱ የጌታ ደቀ መዛሙርት አንዱ የሆንኩት እኔ ማቴዎስ የጻፍኩት ነው" ብሎ አይደለም። ለማቴዎስ ወንጌል **"የማቴዎስ ወንጌል"** የሚለውን ርእስ የሰጠችው ቤተ ክርስቲያን ናት። የቅዱስ ማርቆስ ወንጌልም ሲጀምር "የእግዚአብሔር ልጅ የኢየሱስ ክርስቶስ ወንጌል መጀመሪያ" ብሎ ነው እንጂ "እኔ ማርቆስ የጻፍኩት ወንጌል ነው" ብሎ አይጀምርም። ማር. 1፡1 የማርቆስ ወንጌልን ቅዱስ ማርቆስ የጻፈው መሆኑን የነገረችንና "የማርቆስ ወንጌል" የሚለውን ርእስ የሰጠችው ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት።

የቅዱስ ሉቃስ ወንጌልን በተመለከተም እንደዚሁ ነው። "የከበርህ ቴዎፍሎስ ሆይ፤ . . . ስለ ተማርኸው ቃል እርግጠኑን እንድታውቅ በጥንቃቄ ሁሉን ከመጀመሪያው ተከትዬ በየተራው ልጽፍልህ መልካም ሆኖ ታየኝ" ብሎ ቴዎፍሎስ ለተባለ ሰው የጻፈለት መሆኑን ይናገራል እንጂ ጸሐፊው ሉቃስ የተባለ ሰው ስለመሆኑ አንድም ቦታ ላይ አይናገርም። ሉቃ. 1፡1-4 ይህ ወንጌል ከሰባ ሁለቱ አርድዕት አንዱ በሆነው በቅዱስ ሉቃስ የተጻፈ መሆኑን የነገረችንና ለወንጌሉም "የሉቃስ ወንጌል" የሚል ርእስ የሰጠችው ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት።

ታዲያ እነዚህ ወንጌላውያን በእነርሱ ስም የሚጠሩትን ወንጌሎች የጻፉ ስለመሆናቸው ራሳቸው ያልጻፉ ከሆነ፣ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚሉ አካላት፣ እነዚህ ወንጌሎች በስማቸው በተጠሩባቸው ወንጌላውያን የተጻፉ መሆናቸው እንዴት እንደ ታወቀ ሊነግሩን ይችላሉን? እውነተኞቹ ወንጌላውያን ከጻፏቸው ወንጌሎች ይልቅ ግኖስቲኮቹ ጽፈው ያሰራጯቸው የነበሩት የእነ "የቶማስ ወንጌል"፣ "የማትያስ ወንጌል"፣ "የእንድርያስ ወንጌል"፣ "የፊልጶስ ወንጌል" እና መሰሎቻቸው የጸሐፊያቸው ስም ማን መሆኑን በግልጽ ይናገሩ ነበር። ታዲያ የእነ "የእንድርያስ ወንጌልን"፣

“የፊልጶስ ወንጌልን” ሳንቀበል የማቴዎስ ወንጌልን ለምን ተቀበልን? የተቀበልነው “የማቴዎስ ወንጌል እውነት ስለሆነ ነው” የሚል ቢኖር፣ እውነት መሆኑን ማን ነገረህ? እነዚያንም'ኮ እውነት ናቸው ብለው የሚያምኑባቸው ነበሩ። የግኖስቲኮቹ መጻሕፍትም ይሰራጩ የነበሩት “ቅዱስ መጽሐፍ ናቸው” ተብለው ነበር።

ደግሞስ እውነቱ የማቴዎስ ወንጌል መሆኑን ማን ነገረን? እንዴትስ እርግጠኞች ሆንን? ቀድመን የግኖስቲኮቹ ወንጌል ደርሶን ቢሆን ኖሮ ትክክል አለመሆኑን በምን መሥፈርት እናውቅ ነበር? ትክክለኛውን ወንጌል ካወቅን በኋላ ባገኘነው እውቀት ተመሥርተን በምንወስነው ውሳኔ እርሱ ሳይኖረን እንወስነው የነበረውን ነገር ማወቅ እንችልምና! ለዚህም ምንም ስህተት ቢሆንም ቅሉ፣ መጀመሪያ ላይ ያገኙትን የእምነት መጽሐፍና እምነት በጭፍኑ ተቀብለው አምነው የሚኖሩ በቢሊዮን የሚቆጠሩ የዓለማችን ሕዝቦች ተግባራዊ ምስክሮች ናቸው። ስለዚህ ከአርባ በላይ የነበሩትን የግኖስቲኮችን “ወንጌል” ሳይሆን አራቱን የማቴዎስን፣ የማርቆስን፣ የሉቃስንና የዮሐንስን ወንጌል ብቻ እንድንቀበል በማድረግ ከዚህ ጉድ ያወጣችን ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት።

**“መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ” ብለው የሚያስተምሩ ወገኖች እስኪ እነዚህን ጥያቄዎች ይመልሱ፡-**

- የማቴዎስ ወንጌል በውስጡ የያዘው ቃል የተቀደሰ የእግዚአብሔር ቃል መሆኑን በምን አረጋገጣችሁ? “ቃሉ እውነት ስለሆነ ነው” የምትሉ ከሆነ፣ ቃሉ እውነት መሆኑን በምን እንዳረጋገጣችሁ ንገሩን!
- የማቴዎስ ወንጌልን ከ12ቱ ሐዋርያት አንዱ የሆነው ማቴዎስ ወንጌላዊ የጻፈው መሆኑንስ በምን አረጋገጣችሁ? ከመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ውስጥ የማቴዎስ ወንጌል በማቴዎስ ወንጌላዊ የተጻፈ ስለመሆኑ የሚናገር ሌላ መጽሐፍ አለ? ትክክለኛ የእግዚአብሔር ቃል ስለመሆኑስ የሚናገር ሌላ መጽሐፍ አለ? ካለ አሳዩን!

**እዚህ ላይ አንዳንዶቹ** “በመጽሐፍ ቅዱስ ያመንነው የእግዚአብሔር ቃል ስለሆነ ነው” ብለው ለመመለስ ይሞክራሉ። ከዚያ ቀጥሎ ግን “መጽሐፍ ቅዱስ የእግዚአብሔር ቃል መሆኑን በምን አወቃችሁ?” ሲባሉ “መጽሐፍ ቅዱስ ስለሚናገር ነው” ብለው እንደገና ጥያቄውን መልስ አድርገው ይናገራሉ። ይህም ማለት ሐሳባቸው እንደዚህ የሚል ነው፡- **“መጽሐፍ ቅዱስ የእግዚአብሔር ቃል ነው። መጽሐፍ ቅዱስ የእግዚአብሔር ቃል በመሆኑ፣ በውስጡ ያለው የእግዚአብሔር ቃል መሆኑን ይመሰክራል። ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስ የእግዚአብሔር ቃል ነው።”** ይህ ግን የነገር

አዙሪት ነው። በዚህ ሐሳብ ውስጥ መደምደሚያው ከመነሻው ውስጥ አለ። ስለዚህም ሐሳቡ ፍሬ የሌለውና ኢምክንያታዊ ነው። ይልቁንም ይህ አካሄድ ይህን የመሰለውን የእነዚህን ሰዎች ሞኝነትና ኢምክንያታዊነት ለሚመለከቱ ኢአማንያን መጽሐፍ ቅዱስን ለመንቀፍ እንደ መግቢያ ይሆናቸዋል።

እንዲያው ወደ ሕሊናቸው ቢመለሱና እውነቱን ቢናገሩ የማቴዎስ ወንጌል የተጻፈው በማቴዎስ መሆኑን፣ የተቀደሰ የእግዚአብሔር ቃል የያዘ መሆኑን፣ የማቴዎስ ወንጌል የሚል መጠሪያ የተሰጠው መሆኑን ያወቁት ከቤተ ክርስቲያን ነው። የማቴዎስ ወንጌልንም ሆነ ሌሎቹን ቅዱሳት መጻሕፍት አሁን በእጃቸው ላይ እንዲኖሩ ያስቻለቻቸው ቤተ ክርስቲያን ናት እንጂ እያንዳንዳቸው ወደ ኋላ ሁለት ሺህ ዓመታትን ተመልሰው እንደ አዲስ የማቴዎስ ወንጌል በማቴዎስ የተጻፈ መሆኑን፣ የግኖስቲኮች ሳይሆን የቤተ ክርስቲያንን አስተምህሮ የያዘ መሆኑን አጥንተው እየደረሱበትና ለራሳቸው እየወሰኑ አይደለም። ታዲያ ይህን የመሰለውን ከራሱ ከመጽሐፉ ውጭ የሆነ እና ከቤተ ክርስቲያን ትውፊት የተገኘ መሠረታዊ ማስረጃ እየተቀበሉ፣ እንደገና መልሰ "መጽሐፍ ብቻ" ለምን ይላሉ? ራሱን መጽሐፍ ቅዱስን ለማግኘት እንኳ የመጽሐፍ ቅዱስ ባለቤት የሆነችው ሐዋርያዊት ቤተ ክርስቲያን ያስፈለገች ከሆነ፣ መጽሐፉን በትክክል ለመረዳትስ ለምን አታስፈልግም?

የግኖስቲኮቹን የፈጠራ መጻሕፍት አንጓላና አበጥራ ጥላ እውነተኛውን የእርሷን እምነትና ትምህርት የያዙትን ወንጌሎች ለይታ የሰጠችንና የጠበቀችልን ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት።[9] ቤተ ክርስቲያን ባትኖር ኖሮ መጻሕፍቱ ራሳቸው ከግኖስቲኮች የመጻሕፍት የገለባ ክምር ውስጥ ገብተው ተደብቀው ሊቀሩ ይችሉ ነበር። ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስን ከመናፍቃን መጻሕፍት ለይታ አበጥራና አንጠርጥራ የመረጠቻቸው፣ ከዚያም በአንድ ላይ የሰበሰበቻቸው ሐዋርያዊት ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት። ስለዚህ ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስ የተጻፈባት ዐውድ ናት፣ ከመናፍቃን መጻሕፍት ለይታ የመረጠቻቸውና የጠበቀቻቸውም እርሷ ናት። መጻሕፍቱም የእርሷን እምነትና ትምህርት ይመሰክራሉ፣ ይጠብቃሉም። ስለሆነም መጻሕፍቱን ብቻ ነጥሎና አንጠልጥሎ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ማለት

[9] ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን መጻሕፍቱን ለይታ ቀኖናዊ አደረገቻቸው ማለት በራሳቸው የሌላቸውን ነገር ሰጠቻቸው ማለት አይደለም። ይህም ማለት በውስጣቸው ያለው ሐሳብ አምላካዊ ሐሳብ ስለሆነና የእግዚአብሔር እስትንፋስ ስለሆኑ ያንን እውቅና ሰጠች ማለት ነው እንጂ እርሷ እንደዚያ አደረገቻቸው ማለት አለመሆኑን መገንዘብ ይገባል። ሆኖም ግን እነዚያ ቢሆኑም ቅሉ መጻሕፍቱ ቀኖናውያኑ መጻሕፍት እኛ ነን ብለው ራሳቸው በራሳቸው ተጠራርተው አልተሰባሰቡም፣ ከሐሰተኞቹም የለየቻቸውና ከብረዛ የጠበቀቻቸው ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት ለማለት ነው። ያንን አምላካዊነታቸውን ያለ መቸገርና መጠራጠር እንድናውቅ ያደረገችው እርሷ ናት ማለት ነው። እንደዚሁም የወንጌል ጸሐፊዎች ራሳቸው የቤተ ክርስቲያን አካላት ሆነው በውስጧ ኖረው የጻፉ ስለሆኑም ነው። ከእርሷ ውጭ የሆኑ ሰዎች የጻፉትን መርምራ ያጸደቀችና የተቀበለች ሳትሆን በእርሷ ውስጥ አካላቷ የሆኑት ወንጌላውያን የጻፉትን የእርሷ ካልሆነው የለየች ናት።

ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ የተገኘበትንና የመጣበትን ታሪካዊ እውነታ ካለማወቅ፣ ወይም ለማወቅ ካለመፈለግ የመጣ የቅርብ ዘመን የፈጠራ ሐሳብ ነው።

**የመጽሐፍ ቅዱስ ቀኖና እስከ አራተኛው (4ኛው) መቶ ዓመት ድረስ አልተጠናቀቀም ነበር።**

እዚህ ላይ ወደ ዝርዝር ታሪኩ ባንገባም እስከ 4ኛው መቶ ዓመት ማብቂያ ድረስ በትክክል በሐዋርያት የተጻፉት መጻሕፍት የትኞቹ ስለ መሆናቸው ብዙ ውጣ ውረዶችና ልዩነቶች ነበሩ። በአንዳንዶቹ አካባቢዎችና አብያተ ክርስቲያን የነበረው የመጽሐፍ ቅዱስ ቀኖና ውስጥ በኋላ ላይ ከቀኖና የወጡ መጻሕፍት ነበሩባቸው። ለምሳሌም ኖላዊ ዘሄርማስ (The “shepherd” of Hermas)፣ የበርናባስ መልእክት፣ እና ዲድስቅልያ እንደ መጽሐፍ ቅዱስ ቀኖናውያት መጻሕፍት ይቆጠሩ ነበር፣ በሥርዐተ አምልኮወቅትም በጉባኤ ይነበቡና ሕዝቡ እንዲሰማቸው ይደረጉ ነበር።[10] እንዲያውም ጥንታዊ የሐዲስ ኪዳን መጽሐፍ ቅጂ በሚባለው ኮዴክስ ሲናይቲከስ (Codex Sinaiticus) ውስጥ እነዚህ ሁለቱም የመጨረሻዎቹ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ሆነው ይገኛሉ። ከእነዚህም በተጨማሪ የቀሌምንጦስ ዘሮም የመጀመሪያው መልእክት በብዙ አብያተ ክርስቲያናት ዘንድ ከመጽሐፍ ቅዱስ ቀኖናውያት መጻሕፍት እንደ አንዱ የሚቆጠር ነበር።

በሌላ በኩል ደግሞ በኋላ ላይ ቀኖናዊ ተደርገው ከተቆጠሩት መጻሕፍት መካከል በሁሉም አብያተ ክርስቲያን ዘንድ በወጥነት ቀኖናዊ መጽሐፍ ተደርገው የማይቆጠሩ ነበሩ። ለምሳሌም የዕብራውያን መልእክት በሁሉም አብያተ ክርስቲያናት ዘንድ ቅዱስ ጳውሎስ የጻፈው መሆኑና ቀኖናዊ ተቀባይነቱ ወጥ አልነበረም። የዮሐንስ ራእይንም ለብዙ ዓመታት ያህል ከመጽሐፍ ቅዱስ ቀኖናቸው ውስጥ ያላስገቡ አብያተ ክርስቲያን ነበሩ። ራእየ ዮሐንስ ላይ ጥያቄ የተነሣው ወደ ኋላ ላይ የነበረ ሲሆን እርሱም ሞንታኒስቶች (Montanists) እና ቺሊያስቶች (Chiliasts) ራእየ ዮሐንስን አላግባብ ከመጠቀማቸው የተነሣ የተፈጠረው አጸፌታዊ ተቃውሞ (Reaction) ነበር። ስለሆነም ራእየ ዮሐንስ ቀኖናዊነቱ የተረጋገጠው ዘግይቶ ነበር።

አሁን በሐዲስ ኪዳን ስብስብ ውስጥ ካሉት 27ቱ መጻሕፍት መካከል የያዕቆብ መልእክት፣ የይሁዳ መልእክት፣ 2ኛ የጴጥሮስ መልእክት፣ 2ኛ የዮሐንስ መልእክት፣ 3ኛ የዮሐንስ መልእክት፣ እና ራእየ ዮሐንስ በአንዳንድ ቦታዎች ዘንድ ከመጀመሪያው ጀምሮ ቀኖናዊ ተቀባይነት የነበራቸው ሲሆን በሌሎች አንዳንዶች ቦታዎች ዘንድ ደግሞ ቀኖናዊ ተቀባይነታቸው ወጣ ገባ ነበር። በአጠቃላይ፣ ቤተ ክርስቲያን እስከ

[10] Henry G. Graham, *Where We Got the Bible: Our Debt to the Catholic Church*, pp. 34-35.

4ኛው መቶ ዓመት ድረስ የመጽሐፍ ቅዱስ ቀኖናዋ አላለቀም ነበር። ይህም ማለት ሙሉው መጽሐፍ ቅዱስ በጽሑፍ መልክ በአንድ ላይ አልነበራትም ማለት ነው፤ ይህም ማለት እስከዚያ ዘመን የነበሩት ክርስቲያኖች ትውፊትን ይጠቀሙ ነበር ማለት ነው።

በሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ ቅዱሳን ሐዋርያት ለቤተ ክርስቲያን ያወረሷትን የመጻሕፍት ዝርዝርና ቁጥር (ብዛት) የያዘ የተደነገገ ቀኖና ስለመኖሩ ፍንጭ አይሰጥም። ሁሉን በጥበብ የሚያደርግ እግዚአብሔር የመጻሕፍቱ ዝርዝርና አጠቃላይ ቀኖናዊ ነገሩ ተፈጥሯዊ በሆነ ሁኔታ ቀስ በቀስ በሂደት እንዲመጣ አደረገ እንጂ ገና ከመጀመሪያው ቁርጥ ያለ ቀኖና ራሱ ጌታችንም አልደነገገም፤ ሐዋርያቱም እንደዚያ አላደረጉም። ምክንያቱም በሥጋው መቆረስ በደሙ መፍሰስ የመሠረታት ቤተ ክርስቲያን የምትመራው በመንፈስ ቅዱስ ሕይወትነት እንጂ የግድ መጽሐፍ ላይ ብቻ ተንጠልጥላ አይደለምና።

በመጻሕፍቱ የቀኖና ሂደት ላይ ከቦታ ቦታ ልዩነቶች ይታዩ የነበረ ቢሆንም፤ ውጣ ውረድ ቢገጥመውም፤ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ግን የእግዚአብሔርን የማዳን ጸጋ እየሰበከችና አምነው ለሚቀርቡ ሁሉ ያን ጸጋ እየናኘች የእግዚአብሔር ልጆችን እያፈራች ነበር። በእነዚያ ሁሉ ዘመናት የእውነት ዐምድና መሠረት የሆነችው ሐዋርያዊት ቤተ ክርስቲያን ሰማዕታትን፣ ጻድቃንን፣ ሊቃውንትንና መሰል የሃይማኖት አርበኞችን እያፈራች ነበር። የመጽሐፍ ቅዱስ ዝርዝርና ቁጥር ተሰፍሮና ተለክቶ አይታወቅም ማለት የቤተ ክርስቲያን ትምህርት አይታወቅም ማለት አይደለምና፤ መጻሕፍቱም የተጻፉት ካለው የቤተ ክርስቲያን ትምህርት ዋና ዋናውንና ሊጻፍ የሚችለውን ያህል ቀድተው ለማጠጣት እንጂ ቤተ ክርስቲያንን ሊተኩ አይደለምና። ወንጌላዊው "ኢየሱስም ያደረገው ብዙ ሌላ ነገር ደግሞ አለ፤ ሁሉ በእያንዳንዱ ቢጻፍ ለተጻፉት መጻሕፍት ዓለም ራሱ ባልበቃቸውም ይመስለኛል" ብሎ የገለጠው ይህንኑ አይደለምን? ዮሐ. 21:25 በመጽሐፍ ላይ ብቻ እንድንመሠረት የእግዚአብሔር ሐሳብ ቢሆን ኖሮ ዐሠርቱን ትእዛዛት በጽላት ላይ "በእጆቹ ጽፎ" እንደ ሰጠን፣ በሐዲስ ኪዳንም እንዲሁ መጽሐፍ ከሰማይ አውርዶ ሊሰጠን ይችል ነበር።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ከመጻሕፍት ቀኖና አንጻር የሚገጥመውን ችግር በቀላሉ ለማየት ይህን ጥያቄ እንጠይቅ፡- "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ መርቅያንን ሊሞግተውና ስህተት ነህ ሊለው የሚችለው እንዴት አድርጎ ነበር? መርቅያን የተባለው ግኖስቲካዊ መናፍቅ በ150 ዓ. ም. ገደማ ላይ፣ መጽሐፍ ቅዱስ ነው ብሎ የወሰነው የሉቃስ ወንጌልን (ያውም በየጊዜው ደስ እንዳለው እየቆረጠና እየቀጠለ)፣ እና የቅዱስ ጳውሎስን አሥሩን መልእክታት ብቻ የያዘ ነበር። "መጽሐፍ

ቅዱስ ብቻ" ብሎ የሚያምን ሰው፣ መርቅያንን "ልክ አይደለህም" ብሎ ሊከራከረው የሚችለው እንዴት አድርጎ ነው? የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት እነዚህ ብቻ (11ዱ ብቻ) ሳይሆኑ 27 መሆናቸውን ማሳመን የሚችለው በምን ማስረጃ ነው? መርቅያን ያልተቀበላቸው ሌሎች የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት መኖራቸውን በምን ያውቃል? "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው አቋሙና እምነቱ ጸንቶ ለሚያምን ሰው ይህን መሰሉን ሐሳብ መቃወም አይቻለውም። ምክንያቱም ሐዲስ ኪዳን የሚይዛቸው መጻሕፍት ስንት እና እነ ማን ስለመሆናቸው ራሱ መጽሐፉ አይናገርምና።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው አስተምህሮ መሠረት ከተሄደ አንድ ክርስቲያን በእጁ ያሉት መጻሕፍት ሊኖሩት የሚገባቸውን መጻሕፍት ሙሉ በሙሉ የያዘ ስለመሆን አለመሆኑ በምንም መንገድ እርግጠኛ ሊሆን አይችልም። ሆኖም ይህ የቀኖና መጻሕፍት ዝርዝር፣ የተደረሰበት መንገድ ምንም ይሁን ምን፣ የመጽሐፍ ቅዱስ አካል አይደለም። እንዲህ ያለ የመጻሕፍት ዝርዝር በራሱ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የለም፣ ቢኖርም እንኳ ይህ ዝርዝር ራሱ ትክክል መሆኑ በምን ይረጋገጣል? በየትኛውም አቅጣጫ ብንዞር በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያሉት መጻሕፍት የእግዚአብሔር መንፈስ ያለባቸው መጻሕፍት መሆናቸውን እና መጻሕፍቱም እነርሱ ብቻ መሆናቸውን የሚያረጋግጥ ከራሱ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ አካል ያስፈልጋል። ይህች አካል ደግሞ ሌላ ማንም ሳትሆን ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት። የመጻሕፍቱን ዝርዝርና ዓይነት የመረጠችውና ቁጥራቸውን የወሰነችው ራሳቸው መጻሕፍቶቹ ሳይሆኑ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ናት።

ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ፣ አንድ ሰው የትኞቹ መጻሕፍት በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሚካተቱ ስለመሆናቸው በእርግጠኛነት ሊያውቅ የሚችለው እንዴት አድርጎ ነው? የሚል ከባድ ፈተና ከፊቱ ይደቅንበታል። ይህን ሊነግረው የሚችል ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ያለ አካል ከሌለ በስተቀር ማንም ይህን በእርግጠኛነት ሊያውቅ አይችልም። ይህን የምናውቅ ከሆነና የታወቀ ከሆነ ደግሞ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ፈረሰ ማለት ነው።

ከዚህም ጋር "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ተጨባጭ እውነታዎችን የዘነጋ ነው። መጽሐፍ ቅዱስ እንዲሁ ከሰማይ ተጠቅልሎ ከፊታችን ላይ የወረደ መጽሐፍ አይደለም። ሲጻፍ፣ ሲሰባሰብ፣ ቀኖናዊ ሲደረግ፣ ከዚያም ከእናት ቋንቋዎቹ ከዕብራይስጥና ከግሪክ ወደ ተለያዩ ቋንቋዎች ሲተረጎም፣ በመተርጉማን መጻሕፍት አባቶች ሲብራራና ሲተረጎም፣ . . . ብዙ ሰዎች ተሳትፈውበታል፣ ደክመውበታል። ያለ እነዚህ አባቶችና ሊቃውንት ድካምና ጥረት መጽሐፍ ቅዱስ እንዲሁ ብቻውን ሕዝቡ በሚረዳበት ደረጃና መልክ የመገኘት ዕድሉ በጣም ሩቅ ነበር። ስለዚህ

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ ከእውነታ ጋር የማይተዋወቅ ልብ ወለዳዊ ሐሳብ ነው።

ፕሮቴስታንቶችም የሚጠቀሙበት የሐዲስ ኪዳን የመጻሕፍት ቀኖና በእነ ቅዱስ አትናቴዎስ ሐዋርያዊ፣ በእነ ቅዱስ ሄሬኔዎስ፣ እና እነዚህን በመሰሉ አባቶች የተለዩና የተቀነኑ ናቸው። ሆኖም እነዚህ የመጽሐፍ ቅዱስን ቀኖና የሠሩት አባቶች እምነትና አስተምህሮ ከፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ የተለየ ነው። ስለ መዳን ምንነት፣ ሰው የሚድነው እንዴት እንደሆነ፣ በጥምቀት ላይ፣ በቁርባን ላይ፣ በክህነት ላይ፣ ካላቸው አቋምና አስተምህሮ በጣም የተለየ ነው። ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች እነዚህ አባቶች የመረጧቸውን መጻሕፍት እየተጠቀሙ እምነታቸው ከእነዚያ አባቶች የተለየ ከሆነ ስህተቱ የማን ነው ሊሉ ነው? መቼም የተሳሳቱት እነዚያ አባቶች ናቸው እንጂ እኛ አይደለንም ማለታቸው አይቀርም ይሆናል። እንዲህ የምንለው ሉተር፣ ካልቪንና ሌሎቹም የተሐድሶ ተከታዮች በይፋ ያሉት እንደዚያ ስለሆነ ነው።

መጻሕፍትን የመረጡትና የቀነኑት እነዚያ አባቶች እምነታቸው ስህተት ከነበረ እነርሱ የመረጧቸው መጻሕፍትም ስህተት ናቸው ማለት ነዋ! ምክንያቱም መጻሕፍቱን የመረጧቸው ከሐዋርያት የተቀበልነው አስተምህሮ ነው በሚሉት እምነታቸው መስፈርትነት ነበርና። የመረጧቸው መጻሕፍት ስህተት ከሆኑ ደግሞ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚሉ ፕሮቴስታንቶች በእነዚህ የተሳሳቱ መጻሕፍት ላይ ብቻ የተመሠረቱ ስለሚሆኑ እነርሱም እምነታቸው ትክክል ሊሆን አይችልም። በአንጻሩ የተሳሳትነው እኛ እንጂ እነርሱ አይደሉም ካሉ ደግሞ መልካም ነው፣ እውነቱም ይኼ ነው። ስለዚህም ወደ እነዚያ አባቶች አስተምህሮና እምነት ተመለሱ ብለን በትሕትና እንማልዳቸዋለን።

የቤተ ክርስቲያን አባቶች የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን የመረጡበትና ቀኖናውያት ናቸው ብለው የተቀበሉበት መሠረታዊ መለኪያቸው የነበረው "የነገረ ሃይማኖታዊ አስተምህሮ ይዘት (the Content of the Faith)" ነበር። ቤተ ክርስቲያን ሐዋርያዊ የሆነውን እምነት የያዙት እንደመሆኗ ከዚህ እምነቷ የማይስማማ ምንም ነገር ሐዋርያዊ አለመሆኑን ስለሚያውቁ ከግኖስቲኮች የፈጠራ ድርሰቶች ለይተው ዛሬ ሐዲስ ኪዳን በሚባለው መድበል ውስጥ የሚገቡትን መጻሕፍት የመረጡበት ቀኖና ይህ ከሐዋርያት የተቀበሉት የአስተምህሮና የሕይወት ትውፊት ነበር።

ይህ እውነተኞቹን መጻሕፍት በሐዋርያት ስም ተጽፈው ከነበሩት ከሐሰተኞቹ መጻሕፍት የመምረጥ ሂደት ምን ይመስል እንደ ነበር እንደ ማሳያ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፊው አውሳብዮስ ከጻፈው ውስጥ የሚከተለውን እንመልከት።

የቤተ ክርስቲያን ታሪክ ጸሐፊው አውሳብዮስ፣ ሴራፒዮን የተባለ ብዙ ጽሑፎችን የጻፈ የቤተ ክርስቲያን አባት ስለ ጻፋቸው ድርሰቶች ሲዘረዝር፣ ሴራፒዮን ከጻፋቸው መካከል አንዱ **"የጴጥሮስ ወንጌል"** በሚሉት መጽሐፍ ላይ የጻፈው ድርሰት መሆኑን ይገልጻል። አውሳብዮስ በመቀጠልም ሴራፒዮን ስለ ጻፈበት ምክንያት ሲገልጽ እንዲህ ይላል፡-

> [ሴራፒዮን] ይህን ድርሰት የጻፈው ይህ በጴጥሮስ ስም የሚጠራው ወንጌል [የጴጥሮስ ወንጌል] በውስጡ ከያዛቸው የስህተት ትምህርቶች የተነሣ ሮሰስ በሚባል አጥቢያ ካሉ ክርስቲያኖች ውስጥ ኢኦርቶዶክሳዊ ወደ ሆነ አስተምህሮ የገቡ አንዳንዶች በመኖራቸው ምክንያት፣ ይህ መጽሐፍ [የጴጥሮስ ወንጌል] የያዛቸውን የስህተት ትምህርቶች ስህተትነታቸውን ለማሳየት ነው።

ከዚያም አውሳብዮስ ይቀጥልና ስለ መጽሐፉ ያለውን ሐሳብ ለማሳየት ይሆን ዘንድ፣ "ሴራፒዮን በመጽሐፉ ውስጥ ከጻፈው ትንሽ ማሳያ እንመልከት" ይልና እንዲህ ይቀጥላል፡-

> "ሴራፒዮን እንደሚከተለው ጽፏል፡-
>
> ወንድሞች ሆይ፣ እኛ ጴጥሮስንና ሌሎቹንም ሐዋርያት የክርስቶስ ሐዋርያት እንደመሆናቸው እንቀበላቸዋለን፣ ሆኖም የእነርሱ ሳይሆኑ በእነርሱ ስም የሚሰራጩትን መጻሕፍት ግን ውድቅ እናደርጋቸዋለን እንጂ አንቀበላቸውም፤ ከእነርሱ ለእኛ የተላለፈልንና የተቀበልነው እንደዚህ ያለ ነገር አለመኖሩን እናውቃለንና።[11] . . . በጴጥሮስ ስም ከተሰየመው ከዚህ ወንጌል ውስጥ ሲነበብ በውስጡ የመርቅያን ኑፋቄ ይዘት አለበት። ይህን ወንጌል መጀመሪያ ይጠቀሙበት ከነበሩትና በትጋት ካጠኑት ከዶሴቲኮች አገኘነውና አነበብነው። ስናነበውም ከመድኃኒታችን አስተምህሮ ጋር ተስማሚ የሆኑ ብዙ ነገሮችን አገኘንበት። ሆኖም በዚያ ላይ የተጨመሩና ተቃራኒ የሆኑ ነገሮችንም አግኝተንበታል። እነዚህንም [የተጨመሩትንና ተቃራኒ የሆኑትን] አመልክተናችኋል።[12]

የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ተለይተው የተመረጡበትና የተወሰኑነበት "ቀኖና" ትውፊታዊው የቤተ ክርስቲያን እምነትና ሕይወት ነው። በሐዋርያት ስም ተጽፈናል ይሉ ከነበሩት ሌሎች ብዙ መጻሕፍት መካከል የተመረጡበት መለኪያ

[11] "For we, brethren, receive both Peter and the other apostles as Christ; but we reject intelligently the writings falsely ascribed to them, knowing that such were not handed down to us." No. 3

[12] Eusebius of Caesarea, *Church History*, Book 6, chapter 12.

"ቀኖና"ም ቤተ ክርስቲያን ከጌታችን በሐዋርያት የተቀበለችው እምነትና ሕይወት (ሐዋርያዊ ትውፊት) ነበር። መጻሕፍቱ ቀኖናዊ መሆን አለመሆናቸው የተመዘነው ቤተ ክርስቲያን ከምታምነው እምነትና ከምትኖረው ሕይወት አንጻር ነበር። ብሩስ ሜትገር የተባለ ሊቅ ይህን በተመለከተ እንዲህ ብሏል፡-

> አንድ መጽሐፍ የሚመዘንበት መለኪያ ነበረው፤ እርሱም ከቤተ ክርስቲያን መርሐ እምነት ጋር የሚስማማ መሆን አለመሆኑ ነበር። ይህም ማለት ያ መጽሐፍ ቤተ ክርስቲያን ከተቀበለችውና ከምታምነው እምነትና አስተምህሮ ጋር የተስማማ ነው ወይስ አይደለም? የሚለው ነበር።[13]

### መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ ያረጋግጣልን?

እውነተኛዎቹ የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ከሐሰተኞቹ መጻሕፍት እንዴት እንደ ተመረጡ በቂና ትርጉም ያለው መልስ ስለሌላቸው፤ ፕሮቴስታንቶች ለዚህ ጥያቄ መልስ ይሆነናል ብለው የሚያቀርቡት "መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ ያረጋግጣል" ("Scripture is self-authenticating") የሚል ማምለጫ የሚመስል መልስ ነው። ይህም ማለት የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት በእግዚአብሔር መንፈስ የተጻፉ ስለመሆናቸው ራሳቸው ለራሳቸው ይመሰክራሉ ማለታቸው ነው። በእርግጥ የመጽሐፍ ቅዱስ በእግዚአብሔር መንፈስ የተጻፈ መሆን በራሱ በጣም ግልጽ ነው፤ በዚህ እንስማማለን። ሆኖም መጻሕፍቱ ይህን ራሳቸው ለራሳቸው የሚገልጡ ግን አይደለም። ነገሩ እንደዚያ ቢሆን ኖሮ የቀኖና መጻሕፍት ጉዳይ ሦስትና አራት መቶ ዓመታትን ባልወሰደና ያን ያህል ብዙ ባላደከመ ነበር። እኛ ከእነዚያ አባቶቻችን በእውቀትም በጸጋም የበለጥን ነን በሚል ትዕቢት ከተያዘ ሰው በስተቀር ለእነዚያ አባቶቻችን ቀላል ያልነበረው ጉዳይ ለእኛ የማንም እርዳታ የማያስፈልገውና በግልጽ የታወቀ ጉዳይ ሊሆንልን አይችልም።

ሆኖም የዚህ አስተሳሰብ መሠረታዊ ችግር የቤተ ክርስቲያን ታሪክ አለማወቅ ነው። ትንሽም ቢሆን በወፍ በረር እንኳ የቤተ ክርስቲያንን ታሪክ ለሚያውቅ ሰው "መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ ያረጋግጣል" የሚሉት ይህ ሐሳባቸው ምን ያህል ከእውነትም ከእውቀትም የራቀ መሆኑን መገንዘብ ይችላል። የፕሮቴስታንት ተሐድሶዎች ትልቁ ችግራቸው ቤተ ክርስቲያን ከእነርሱ በፊት የነበሩትን ዘመናት እንዴት እንደ ኖረች አለማወቃቸውና ለማወቅም አለመፈለጋቸው ነው። እንዲያውም ከዘመነ ሐዋርያት አንሥቶ ቤተ ክርስቲያን የተጓዘችበትን የሕይወት ጉዞ ማወቅ እነርሱ የሚሏቸውን ነገሮች ስለሚያፈርስባቸው ታሪክን አምርረው ይጠላሉ፤ ያንቋሽሻሉ፤ ተከታዮቻቸውም ታሪክን እንዳያውቁ አጥብቀው ያስተምራሉ።

[13] Dr. Bruce M. Metzger, In *The Case for Christ: A Journalist's Personal Investigation of the Evidence for Jesus*, Lee Strobel, 2016.

ፕሮቴስታንቶች እንደሚሉት የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ራሳቸውን በራሳቸው የሚያረጋግጡ ከሆኑ፣ የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቀኖና ተወስኖ እስኪታወቅ ድረስ ለምን ብዙ መቶ ዓመታትን (400 ዓመታት ገደማ) ወሰደ? የዚህ ምክንያቱ **መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ የሚያረጋግጥ አለመሆኑ ነው::**

ጸሐፊያቸው ማን መሆኑን እንኳ የማይናገሩት የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ራሳቸውን በራሳቸው የሚያረጋጋግጡት እንዴት አድርገው ነው? ለምሳሌ የማቴዎስ ወንጌልን እንውሰድ። ከላይ እንዳየነው የማቴዎስ ወንጌል የተጻፈው ከ12ቱ ሐዋርያት አንዱ በሆነው በማቴዎስ ስለመሆኑ አንድም ቦታ ላይ እንኳ አይናገርም። ታዲያ የማቴዎስ ወንጌል ራሱን በራሱ የሚያረጋግጠው እንዴት አድርጎ ነው? ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ እንኳ ከልዩ ልዩ የመናፍቃን መጻሕፍት እንዴት እንደ ተለየና ቀኖናዊ እንደሆነ ሊያሳውቅ የማይችል ነው። ይልቁንም ልናውቅበት የምንችለውን መንገድ የሚዘጋና ራሱን በራሱ የሚያፈርስ ሐሳብ ነው።

እዚህ ላይ "መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ ያረጋግጣል" የሚሉት የመከራከሪያ ነጥባቸው የትም እንደማያደርስ ሲመለከቱ፡ ፕሮቴስታንቶች **"የማቴዎስን ወንጌል ማቴዎስ ይጻፈው አይጻፈው ማወቅ ለመዳን አስፈላጊያችን አይደለም"** ሊሉ ይችላሉ። ፕሮቴስታንት ወገኖቻችን መሠረታዊ ስህተቶቻቸውና አስተምህሮዎቻቸው መርተው የሚያደርሱበትን ፍጥጥ ያለ የስህተት ድምዳሜ ለመቀበል ሲቸገሩ ብዙውን ጊዜ ለማምለጥ የሚሞክሩት ይህን የመሰለ መላ ቅጥ የሌለው ነገር በማለት ነው። ራሳቸውን ለመደበቅ የሚሞክሩት እንደዚህ በመሰሉና "ጌታ በቂዬ ነው"፣ "ዋናው ጌታ ነው"፣ "በጌታ ድኛለሁ"፣ "የጌታ ልጅ ሆኛለሁ" የሚሉ ከጉዳዩ ጋር ምንም ግንኙነት የሌላቸውን ነገሮች መልሰው መላልሰው በመናገር መሆኑ የተመሰከረላቸው ናቸው። ሆኖም ግን ይህ አባባል ሌላ ፈተና ይጋርጥባቸዋል። በአንድ በኩል ወደ መዳን የሚያደርሰው እውነተኛው ወንጌል መሆኑን እናምናለን እያሉ፣ በሌላ በኩል ደግሞ ሐዋርያው ማቴዎስ የጻፈው እውነተኛው ወንጌል የትኛው መሆኑን ለማወቅ የሚያስችል መንገድ ከሌላቸው፣ የማቴዎስ ወንጌል ነው የተባለው ወንጌል የሐዋርያው ማቴዎስ መሆኑን ወይም አለመሆኑን፣ እናም ትክክለኛ የእግዚአብሔር ቃል መሆን አለመሆኑን ሊያውቁ አይችሉም ማለት ነው።

በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ዘመን በማቴዎስ ስም ይሰራጭ የነበረው መጽሐፍ የማቴዎስ ወንጌል ብቻ አልነበረም። ማቴዎስ ወንጌላዊ ጽፎታል ተብሎ ይሰራጭ የነበረ "የተከራካሪው የቶማስ መጽሐፍ - the book of Thomas the Contender" የሚባል ሌላ መጽሐፍም ነበር። የማቴዎስ ወንጌል የተባለውን መጽሐፍ ከዚህ ዓይነቱና ከመሰል

ሌሎች መጻሕፍት እንዴት መለየት ተቻለ? ፕሮቴስታንቶች እነዚህን የመሰሉ አማብቂኞችን ለማለፍ ወደ 2ኛ ጢሞ. 3፥16 "የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ . . ." ወደሚለው ጥቅስ ለመመለስና ይህንኑ ጥቅስ ለሁሉም ነገር መልስ አድርጎ ለማቅረብ ይሞክራሉ። ሆኖም ይህ ጥቅስ በመጀመሪያ "የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ ይጠቅማል" ይላል እንጂ እነዚህን የእግዚአብሔር መንፈስ ያለባቸውን መጻሕፍት እነ ማን መሆናቸውን ዘርዝሮና ቆጥሮ አይነግረንም። እዚህ ላይ ጥያቄው የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ጠቃሚ ነው አይደለም? ሳይሆን፤ እነዚህ መጻሕፍት የትኞቹ ናቸው? የሚለው ነው። ስለዚህ ይህ ጥቅስ የመጻሕፍቱን ዓይነት ስለማይናገር ለዚህ ጉዳይ መልስ ሊሆን አይችልም።

በዚያውም ላይ ራሳቸው ለራሳቸው የሚመሰክሩና "የእግዚአብሔር መንፈስ አለብን" የሚሉ፤ እንዲሁም አማኞቻቸው እንደዚያ ብለው የሚናገሩላቸው፤ ሆኖም ግን እንደሚሉትና እንደሚባልላቸው ያልሆኑ ብዙ መጻሕፍት በምድራችን ላይ ነበሩ፤ ዛሬም አሉ። መጻሕፍቱ ስለ ራሳቸው እውነተኛነት መናገራቸው ብቻ እውነተኛ አያደርጋቸውም፤ "እኔ ትክክል ነኝና እመኑኝ" ያለንን ሰው ወይም መጽሐፍ ሁሉ አምነን እንቀበለዋለን?

ከአጋንንት ያገኙትን ትምህርት "ከሰማይ ወረደልኝ"፤ "መልአኩ እገሌ ሰጠኝ" እያሉ መጽሐፋቸው "ልዩ ተአምር" መሆኑን የሚናገሩና ይህንንም በመጽሐፋቸው ውስጥ የጻፉ አሉ። ከዚያም አልፎ መጽሐፋቸው ከራሱ ከአምላካቸው በቀጥታ ከሰማይ የወረደ በመሆኑ መጽሐፋቸውን መጠራጠርና ጥያቄ ማንሳት እንኳ ከባድ ችግር የሚያስከትል መሆኑን በውስጣቸው የያዙ መጻሕፍት በምድራችን ላይ አሉ።

ይህ ቀደም ባሉት ዘመናት ብቻ የነበረና ዛሬ ግን የቀረ የድሮ ታሪክ ሳይሆን በቅርብ ዘመናትም እየተከሠተ ያለ ነገር ነው። ለምሳሌም በ1820ዎቹ የተመሠረተው የሞርሞኒዝም (ራሳቸውን "የኢየሱስ ክርስቶስ የመጨረሻው ቀን ቅዱሳን ቸርች - the church of jesus christ of Latter Day Saints" ብለው የሚጠሩት ቡድኖች) መሥራች የነበረው ጆሴፍ ስሚዝ እምነቱን ሲመሠርት የጻፋቸውን ብዙ መጻሕፍትና ራእዮች እርሱና ተከታዮቹ "የተቀደሱና የእግዚአብሔር መንፈስ ያለባቸው ናቸው" ይሏቸዋል። ተከታዮቹም እነዚህን መጻሕፍት የእነርሱ "መጽሐፍ ቅዱስ" አድርገው ይቀበሏቸዋል። መሥራቻቸው ጆሴፍ ስሚዝ መጻሕፍቱን እንዴት እንዳገኛቸው ሲናገር ሞሮኒ የተባለ መልአክ ወደ አንድ ተራራ እንደ ወሰደውና በዚያ ውስጥ ጥንት በነቢያት ተጽፈው ተቀብረው የነበሩ ወርቃማ ጽሑፎችን እንዳገኛቸው ይናገርና መጽሐፎቹም ከእነዚያ የተተረጎሙ ናቸው ይል ነበር። በ1829 ላይ እነዚያን ወርቃማ ጽሑፎች ያዩዋቸው መሆናቸውን የመሰከሩ 11 ሰዎች ነበሩ፤ ከእነዚያ መካከል 3ቱ

መልአክ መጥቶ ነብኝቶናል ይሉ ነበር።[14] ሞርሞኖች ብዙ ሴት ማግባትን ከመፍቀድ እንሥቶ ነገራቸው ሁሉ ከክርስትና መሠረታዊ አስተምህሮ ጋር የሚቃረን ነው። እ. ጎ. አ በ2018 ላይ በዓለም ዙሪያ ወደ 16 ሚሊዮን ገደማ የሞርሞኒዝም ተከታዮች አሉ።[15]

እንዲሁም ባሃ ኡ ላህ የተባለው ኢራናዊ (1817-1892) ከእርሱ በፊት ከተነሡት ሁሉ የበለጠ ሙሉና አብርሆታዊ የሆነ መገለጥ ከእግዚአብሔር ዘንድ ተቀብያለሁ ይል ነበር። ባሃ ኡ ላህ፣ ለእርሱ የተገለጠለት መገለጥ የኢየሱስ ክርስቶስን ትምህርት ተክቶታል ብሎ በድፍረት ይናገር ነበር። ከእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ጋር ቀጥተኛ ውይይት እንዳደረገና ዘርፈ ብዙ ስለ ሆኑ ሃይማኖታዊ ጉዳዮች አዲስ መገለጥን ተቀብያለሁ ይል ነበር። ጽሑፎቹ ዋና ትኩረትና አጽንኦት የሚያደርጉት ፍትሕ፣ አንድነት እና ፍቅር በሚሉ ጉዳዮች ላይ ነው።[16]

እንደዚሁም "ክርስቲያን ሳይንስ - Christian Science" የተባለው እምነት መሥራች የነበረችው ሜሪ ቤከር ኤዲ (1821-1910) ጽሑፎቿን "የእግዚአብሔር መንፈስ ያለባቸው ናቸው" ብላቸዋለች። ሜሪ ቤከር በ1890ዎቹ በአሜሪካ አገር ፈውስ ላይ ትኩረት ያደረገ አዲስ ቸርች መሥርታለች። ዛሬ በዓለም ዙሪያ በ76 አገሮች ውስጥ ወደ 1700 የሚደርሱ የክርስቲያን ሳይንስ ቸርቾች አሉ።[17]

እንግዲህ እነዚህ ማንኛውም ጽሑፍ ስለ ራሱ ቅዱስነትና ከሰማይ የወረደ ስለመሆኑ የፈለገውን ያህል ሊል እንደሚችል ለማሳየት የቀረቡ ጥቂት ማሳያዎች ብቻ ናቸው። አንድ መጽሐፍ ራሱ ለራሱ "የእግዚአብሔር መንፈስ ያለብኝ ነኝ" ማለቱ ብቻ የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት ስለመሆኑ ዋስትና ሊሆን አይችልም። እንዲህ ቢሆንማ ኖሮ በምድራችን ላይ በእውነት ስም የተጻፉ የሐሰት መጻሕፍት ባልኖሩባትና ባልተሰራጩባት ነበር፣ በቢሊዮን የሚቆጠር ሕዝብ እያሳሳቱ ባልኖሩ ነበር። ስለሆነም አንድ መጽሐፍ እርግጠኛና አስተማማኝ በሆነ ሁኔታ የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት ስለመሆን አለመሆኑ ለማወቅ መጽሐፉ ስለ ራሱ ከሚናገረው እና "ነኝ" ከሚለው ውጭ ሌላ ማወቂያ መንገድ ሊኖር ግድ ይላል። ሆኖም ለመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት እውነተኛነት ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ያለ ማረጋገጫና ማወቂያ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው የፕሮቴስታንት አስተምህሮ መሠረት በሩ የተዘጋበት ነው። ስለዚህም የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት እንዴት እንደ ተገኙና እንደ ታወቁ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ሊነግረን አይችልም ማለት ነው።

---

14 "Gospel Topics – Book of Mormon Translation", lds.org, LDS church

15 Dialogue: A Journal of Mormon Thought (31 (2)):1-68

16 Erwin W. Lutzer, *Christ Among Other gods*, pp. 128-129

17 Christian Science Journal, Christian Science Church listings.

ችግሩ ሊነግረን አለመቻሉ ብቻ ሳይሆን ልናውቅ የምንችልበትን መንገድም የሚዘጋብን መሰናክል መሆኑ ነው። የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍትን ቀኖናዊ ሂደት በጥልቀት ያጠና ኤፍ. ኤፍ. ብሩስ የተባለ ሰው ይህን ሁኔታ በተመለከተ እንዲህ ብሏል፡-

> በጥንት ዘመን የሚጻፉ መልእክቶች የሚጀምሩት በጸሐፊው ስም ነበር፤ የቅዱስ ጳውሎስ መልእክቶችም የሚጀምሩት እንደዚያ ነው። ሆኖም ብዙዎቹ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት የጸሐፊዎቻቸውን ስም አይናገሩም፤ የጸሐፊያቸውን ማንነት የማይገልጹና ማን እንደ ጻፋቸው የማይናገሩ ስም አልባዎች ናቸው። ለቴዎፍሎስ የጻፈለት ጸሐፊ ለእርሱ [ለቴዎፍሎስ] የታወቀ ነበር (ሉቃ. 1፡3 ፤ የሐዋ. 1፡1)፡ ሆኖም የጸሐፊው ስም ማን እንደሆነ ግን በሦስተኛው ወንጌል ላይም ሆነ በሐዋርያት ሥራ ላይ አልተጻፈም። ስለዚህ እነዚህ ሁለት መጻሕፍት ለእኛ ጸሐፊያቸው ማን እንደሆነ የማይታወቁ ናቸው። ሆኖም ግን የጻፋቸው ወንጌላዊው ሉቃስ መሆኑን በትውፊት አውቀናል።
>
> በአንድ በኩል አራቱ ወንጌሎች ሁሉም ጸሐፊያቸው ማን መሆኑን በግልጽ የማይናገሩ መሆናቸውን፤ በአንጻሩ ደግሞ በሁለተኛው መቶ ዓመትና ከዚያም በኋላ እንደ አሸን የፈሉትና ሲሰራጩ የነበሩት "ወንጌል" ነን ባዮች ደግሞ በሐዋርያትና ለጌታችን የዓይን ምስክሮች በሆኑ ሰዎች ተጽፈናል ብለው በግልጽ ይናገሩ የነበሩ የመሆናቸውን ነገር ሲያስቡት የሚገርም ነገር ነው። ስለዚህም የቤተ ክርስቲያን አባቶች ውድቅ ካደረጓቸውና ካልተቀበሏቸው ከሌሎቹ መጻሕፍት አንጻር እነርሱ የተቀበሏቸውን የእውነተኛዎቹን ወንጌሎች ሐዋርያዊ እውነተኛነት ማስረዳት አስፈላጊ ሆኖ አገኙት። . . . የማቴዎስ እና የዮሐንስ ወንጌል በእነዚህ ሐዋርያት የተጻፉ መሆናቸው በትውፊት በሚገባ ሆኖ የተረጋገጠ ነበር።[18]

ቅድስት ቤተ ክርስቲያን እውነተኛ የሆኑትን መጻሕፍት እውነተኛ ካልሆኑት ለመለየት ማጣሪያና መመዘኛ አድርጋ የተጠቀመችው መጻሕፍቱ ራሳቸው ስለ ራሳቸው ቅድስና መናገር አለመናገራቸውን ሳይሆን በውስጣቸው የያዙት ትምህርት መሥራቿና ራሷ ኢየሱስ ክርስቶስ "እውነት እውነት እላችኋለሁ" እያለ ካስተማረውና ከእርሱ ከተቀበለችው እውነት ጋር ተስማሚ መሆን አለመሆኑን ነበር። ይህም ማለት መጻሕፍቱ የተለዩበትና የተመረጡበት መመዘኛ ከጌታ የተሰጠው ሐዋርያዊው ትምህርት (Apostolic Teaching) ነበር ማለት ነው። ስለዚህ ከቤተ ክርስቲያን ውጭ መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ገብተው የሚቆጠሩትን መጻሕፍት ለይቶ ለማወቅ በሌላ በምንም መንገድ አይቻልም ነበር። ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው

[18] F.F. BRUCE, *The Canon of Scripture*, 1988, pp. 256, 257.

አስተምህሮ፣ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ እንዴት እንደ ተገኘ እንኳ ካለማወቅ ግዙፍ አላዋቂነት የመጣ የስህተት አስተምህሮ ነው።

በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሚካተቱት እውነተኞቹ መጻሕፍት የትኞቹ ስለመሆናቸው በሰዎች ምርምርና ጥልቅ ጥናት ብቻ ይደረስበታል ማለትም ጉዳዩን አለማወቅ ነው። ፕሮቴስታንቶች የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት እነ ማን መሆናቸውን የተቀበሉት (ያገኙት) ከቤተ ክርስቲያን ሲሆን የተቀበሉት ደግሞ በእምነት ነው እንጂ እያንዳንዱን መጽሐፍ አንብበውና መርምረው "ይህ ልክ ነው፥ መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ይግባ፥ ይህ ልክ አይደለም አይግባ" እያሉ አይደለም። እንዲህ አድርገን ነው ካሉ (አለመሆኑ የታወቀ እውነታ መሆኑ እንደ ተጠበቀ ሆኖ) መጽሐፉን የመረመሩበትና የመረጡበት መለኪያቸው ምንድን ነው?

መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን በመጻሕፍቱ ቀኖናዊነት ዙሪያ ያለውን ጉዳይ ሊፈታው አይችልም። መጻሕፍቱማ እነርሱ ራሳቸው በቀኖና ውስጥ ይካተቱ ወይም አይካተቱ ተብሎ ውሳኔ የሚሰጥባቸው እንጂ ራሳቸው "አስገቡን" ወይም "አታስገቡን" የሚሉ "ሰዎች" አይደሉም። ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ" በሚለው መድበለ ቀኖና ውስጥ የሚገቡትንና የማይገቡትን መጻሕፍት የወሰነችው እናታችን ቤተ ክርስቲያን ናት እንጂ መጻሕፍቱ ራሳቸው በራሳቸው አይደሉም።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚሉ ወገኖችን እስኪ እነዚህን መሠረታዊ ጥያቄዎች እንጠይቃቸው፤

ጥያቄ 1፡- መጽሐፍ ቅዱስ የእግዚአብሔር ቃል መሆኑን በምን አወቃችሁ?

ጥያቄ 2፡- መጽሐፍ ቅዱስ በውስጡ የያዛቸው መጻሕፍት 66 መሆናቸውን በምን አወቃችሁ?

ጥያቄ 3፡- እነዚህ መጻሕፍት የእግዚአብሔር መንፈስ ያለባቸው መሆናቸውን በምን አወቃችሁ?

ምናልባት ለዚህ ለ3ኛው ጥያቄ መልስ ብለው 2ኛ ጢሞ. 3፡17ን ለመጥቀስ ይሞክሩ ይሆናል። ሆኖም ግን 2 ጢሞ 3፡17 "የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ ለትምህርትና ለተግሣጽ ልብንም ለማቅናት በጽድቅም ላለው ምክር ደግሞ ይጠቅማል" ይላል እንጂ እነዚህ መጻሕፍት እነ እገሌ ናቸው ብሎ ዝርዝራቸውን አይናገርም። እንዲሁም የመጻሕፍቱ ብዛት 50 ይሁን 60 ወይም 80 ወይም 100 አንዳችም ፍንጭ አይሰጥም። ለእነዚህ ጥያቄዎች ብቸኛው መልስ እነዚህን ያወቅነውና ያገኘነው ከቤተ ክርስቲያን ነው የሚል ብቻ ነው። ፕሮቴስታንቶች የሚቀበሏቸውን 66 መጻሕፍት ያገኟቸው ከቤተ ክርስቲያን

ነው። ሆኖም ከቤተ ክርስቲያን የተገኘውን ሀብት እየተጠቀሙ መልሰው ቤተ ክርስቲያንን ለመቃወም ይነሣሉ። ይህም "ዘይሴሰይ እክልየ አንሥአ ሰኰናሁ ላዕሌየ - እንጀራዬን የሚበላው እርሱ ተረከዙን በእኔ ላይ አነሣብኝ" ተብሎ የተነገረባቸው ናቸው። ከዚህ ውጭ መጽሐፍ ቅዱስ ራሱ በራሱ አልተሰበሰበም፣ በራሱም አልተገኘም።

ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው አስተምህሮ መሠረት ልንመልሳቸው የማንችላቸው ሁለት መሠረታዊ ጥያቄዎች አሉ። እነዚህም፡-

**አንደኛ፡-** የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ቀኖና ተለይቶ እስኪታወቅ ድረስ የክርስትና አስተምህሮ ምስክርና የመጨረሻ ወሳኝ ሆኖ ሲያገለግል የነበረው ማን ወይም ምን ነበር? የሚለው ሲሆን፣

**ሁለተኛው ደግሞ፡-** ከመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቀኖና መወሰን በፊት የክርስትና አስተምህሮን በተመለከተ የመጨረሻው ተሰሚነት የነበረው አካል የነበረ ከሆነ (ይህ ካልሆነ በዚህ አካል የተወሰነውን የመጽሐፍ ቅዱስን ቀኖናም መቀበል የለባቸውምና)፣ የዚህ አካል ተሰሚነት ልክ የመጽሐፍ ቅዱስ ቀኖና እንደተወሰነ ወዲያውኑ አከተመለት ሊባል የሚቻለው በምን መሠረት ነው?

ስለሆነም መጻሕፍቱን ለይታ የሰጠችንና ከመጻሕፍቱ ቀኖና መወሰን በፊትም ከክርስቶስ ያገኘችውን እውነት ጠብቃ የኖረችውና ለክርስትና ሃይማኖት ተጠያቂዋና ወሳኟ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን እንደ ነበረች ሁሉ መጻሕፍቱ ከተወሰኑ በኋላም መጻሕፍቱን የምንረዳበትን አረዳድና ዐውድ የምትሰጠን እርሷ ናት። ስለሆነም ተሐድሶ ፕሮቴስታንቱ ጸጋ አብ እንዲህ ብሎ የጻፈው ይህን ሁሉ መሠረታዊ ነገር ካለማወቅ መሆኑ ግልጽ ነው፡-

- "ቤተ ክርስቲያን ከቃሉ እንጂ ቃሉ ከቤተ ክርስቲያን አልተገኘም። ቃሉ ፈጠራት እንጂ ቤተ ክርስቲያን ቃሉን አልፈጠረችም።" (ገጽ 209)
- "ከተሐድሶ በፊት የነበረችው ቤተ ክርስቲያን የእግዚአብሔር ቃል የሆነው መጽሐፍ ቅዱስ የሌላት ነበረች። መጽሐፍ ቅዱስ የሌለባት ቤተ ክርስቲያን ማለት ሞተር እንደሌለው መኪና፣ ዘይት እንደሌለው ቀንዲል፣ መሠረት እንደሌለው ቤት ማለት ነው።" (ገጽ 250)

መጽሐፍ ቅዱስ እንዴት እንደ ተገኘ ሁነኛ እውቀት ቢኖረው ኖሮ እንዲህ ባላለ ነበር። የእግዚአብሔር ቃል ያለው መሆን ማለት የታተመና የተጠረዘ "መጽሐፍ ቅዱስ" ይዞ መዞር ማለት አይደለም። የእግዚአብሔር ቃል ያለው ማለት በመጽሐፍ የተጻፈም ሆነ በቃል የተጠና ይሁን፣ ወይም በልብ ጽላት የተጻፈ፣ ያ የእግዚአብሔር

ቃል የሚናገረውን ጸጋ ለማግኘት የሚያስችለውን የቤተ ክርስቲያን ምስጢራት ሐዋርያዊ በሆነ ክህነት መፈጸም ሲቻል ብቻ ነው። ተሐድሶ ፕሮቴስታንት ግን ራሱን ከዚህ አውጥቶ የጣለ ስለሆነ በዋናነት ቃሉ የሌለው ቸርች የተፈጠረው ከተሐድሶ ወዲህ ነው። ስለዚህ **"የእግዚአብሔር ቃል የሆነው መጽሐፍ ቅዱስ የሌላት"** የሆነችው ከተሐድሶ በኋላ እነ ሉተርና መሰሎቹ የፈጠሯቸው ቸርቾች ናቸው።

እንደዚሁም "ቤተ ክርስቲያን ከቃሉ እንጂ ቃሉ ከቤተ ክርስቲያን አልተገኘም። ቃሉ ፈጠራት እንጂ ቤተ ክርስቲያን ቃሉን አልፈጠረችም" የሚለውም ከላይ እንዳየነው ቤተ ክርስቲያንን ካለማወቅ የተነገረ ነው። ቤተ ክርስቲያንን ክጎኑ ባፈሰሰው ደሙና በማየ ገቦው፣ በቆረሰው ሥጋው የመሠረታት፣ ለምግብናዋም ይህን ዕፁብ ድንቅ የሆነ ምስጢር፣ እንዲሁም ቃሉንና መንፈስ ቅዱስን የሰጣት እርሱው ራሱ ነው እንጂ እናንተ "ቃሉ" የምትሉት የተጻፈ መጽሐፍ እስኪጻፍ ድረስ ሳትኖር ቆይታ መጽሐፍ ሲጻፍ ህልውናዋ አንድ ብሎ የጀመረ አይደለችም።

## 3. የመጀመሪያዎቹ ክርስቲያኖች "መጽሐፍ ቅዱስ" አልነበራቸውም።

ቤተ ክርስቲያን ከመጽሐፍ ቅዱስ በዕድሜና በዘመን የምትቀድም መሆኗን አይተናል። የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ከመጻፋቸው በፊት ክርስቲያኖች የነበሩ መሆናቸውን ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ ይናገራል። ለምሳሌም የሐዋርያት ሥራ መጽሐፍ ከጌታችን ዕርገትና ከበዓለ ሃምሳ ጀምሮ ስለ ነበረችው ቤተ ክርስቲያን የመጀመሪያ ሕይወት የሚገልጽ ነው። ክርስቲያኖች መጀመሪያ "ክርስቲያን" ተብለው በአንጾኪያ ሲጠሩ ከሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ አንዳቸውም ገና አልተጻፉም ነበር። ሌላው ቢቀር እነዚያ ክርስቲያኖች በ98 ዓ. ም. አካባቢ እንደ ተጻፈ የሚታመነው ራእየ ዮሐንስና የዮሐንስ ወንጌል መጽሐፍ አልነበራቸውም። ስለዚህ እስከ 98 ዓ. ም. የነበሩ ክርስቲያኖች እኛ ዛሬ በምናውቀው ሁኔታ "መጽሐፍ ቅዱስ" አልነበራቸውም። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" እንደሚሉት ፕሮቴስታንቶች ከሆነና የክርስቲያኖች የትምህርታቸውና የእውቀታቸው ብቸኛው ምንጭ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ከሆነ፣ እነዚያ ሰዎች እንዴት ክርስቲያን ሊሆኑ ቻሉ? እንዴትስ በአንጾኪያ "ክርስቲያን" ተብለው ተጠሩ?

ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ የጻፋቸውን አምስቱን መጻሕፍት ከመጻፉ በፊት በሰማዕትነት የሞቱት እነ ቅዱስ ያዕቆብ ሐዋርያ፣ ቅዱስ ጴጥሮስና ቅዱስ ጳውሎስ፣ ዛሬ እኛ የምናየውን ዓይነት ሙሉ የሆነ መጽሐፍ ቅዱስ ተጽፎ አላዩም። እነርሱ የነበራቸው የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትና የተወሰኑ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት እና ትውፊት ነበር። ታዲያ የክርስትና መሠረቱ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ነው ከተባለ እነዚህ ቅዱሳን

ክርስቲያኖች አልነበሩምን? ከእነዚህም በላይ ደግሞ ገና አንድም የሐዲስ ኪዳን መጽሐፍ ሳይጻፍ፣ በድንጋይ ተወግሮ በሰማዕትነት የሞተው ቅዱስ እስጢፋኖስ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን እንዳቸውንም አላየም። ታዲያ ቅዱስ እስጢፋኖስ "መጽሐፍ ቅዱስ" ስላልነበረው ክርስቲያን አልነበረም ሊባል ነው?

የመጨረሻው የሐዲስ ኪዳን መጽሐፍ (ራእየ ዮሐንስ) የተጻፈው በ98 ዓ. ም. ገደማ እንደሆነ የመጽሐፍ ቅዱስ ምሁራን ይነግሩናል። ፕሮቴስታንቶች እንደሚሉት የክርስቲያኖች የትምህርት ምንጭ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ከሆነ፣ ጌታችን ካረገበት ከ34 ዓ. ም. አንሥቶ እስከ 98 ዓ. ም. ድረስ በነበሩት 60 በላይ ዓመታት ውስጥ የነበሩት ክርስቲያኖች ሙሉው የክርስትና ትምህርት አልነበራቸውም ነበር ማለት ነው? በዚያን ዘመን ውስጥ ለነበሩት ክርስቲያኖች ክርክር ሲፈጠር የመጨረሻው ውሳኔ የሚሰጠው በምን ዳኝነትና ተጠቃሽነት ነበር? "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ለሚሉ አካላት ይህ የማይታለፍ ሸለቆ ነው።

ከዚህም ጋር የዚያን ዘመን ክርስቲያኖች አብዛኞቻቸ ማንበብና መጻፍ የሚችሉ አልነበሩም። ማንበብ የሚችሉትም ሆኑ ሌላው ክርስቲያን፣ ሁሉም የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ተሰብስበው ያሉበት ሙሉ መጽሐፍ ቅዱስ ገዝቶ ወደ ቤቱ እየወሰደ ራሱ ለራሱ እያነበበ የግሉን አረዳድ እንደ መጨረሻ ትክክለኛ አረዳድ ይዞ የሚኖርም አልነበረም። በዚያን ዘመን መጽሐፍ ቅዱስ በእጅ የሚገለበጥ የነበረ በመሆኑ አንድ ላይ ለማድረግ ከጥቅልሉ ብዛት የተነሣ እጅግ አስቸጋሪ ስለነበር በቀላሉ የሚገኝ አልነበረም። ዋጋውም በግለሰብ ደረጃ ቀላል አልነበረም። በአብዛኛው የሚገኘውና የሚቀመጠው በቤተ ክርስቲያን አባቶች፣ በገዳማትና በአብያተ ክርስቲያናት እና በአንዳንድ ባለጸጎች ቤት ነበር። ታዲያ ሕዝበ ክርስቲያኑ ክርስትናን መማርና ማወቅ፣ በተግባርም መኖር እንዴት ቻለ? ሕዝቡ የክርስትናን ሃይማኖት መማርና መኖር የቻለው የቤተ ክርስቲያን አባቶች ጳጳሳት እና ካህናት ክርስትናን ለሕዝቡ ያስተምሯቸው ስለነበር ከእነዚያ አባቶች በመማር እንጂ እያንዳንዱ አንድ አንድ መጽሐፍ ቅዱስ እየወሰደ በግሉ እያነበበና ለራሱ እየተረጎመ አልነበረም።

ቅዱሳን ሐዋርያት ይልኳቸው የነበሩት መልእክታት የሚላኩትም እያንዳንዱ ግለሰብ በየግሉ እንዲያነባቸውና የየራሱን መረዳት ይዞ እንዲቀጥል ሳይሆን ለዚያ ለሚላክለት ቤተ ክርስቲያን የሚላኩ ነበሩ። ከዚያም መልእክቱ ምእመናን በአንድነት በተሰበሰቡበት በቤተ ክርስቲያን ይነበብ ነበር። ቅዱስ ጳውሎስ "ይህ መልእክት ለቅዱሳን ወንድሞች ሁሉ እንዲነበብ በጌታ አምላችኋለሁ" እንዳለ። 1 ተሰ. 5፡27፤ ቆላ. 4፡15 ቅዱስ ጳውሎስ እንዲህ ባለ ሁኔታ መልእክቶቹ በቤተ ክርስቲያን በኅብረት እንዲነበቡ ይላል እንጂ እያንዳንዱ ሰው ለየራሱ ይተረጉማቸው ዘንድ እነዚያ መልእክቶች

በትጋት እንዲገለበጡና ለእያንዳንዱ ክርስቲያን በነፍስ ወከፍ እንዲሰጡ የሚል ትእዛዝ በመልእክቶቹ ሁሉ አንድም ቦታ ላይ የለም።

እነዚያ የመጀመሪያዎቹ ክርስቲያኖች ከላይ እንዳነሣነው መጽሐፍ ቅዱስ በየግላቸው የነበራቸው አልነበሩም። ስለዚህ እነዚያ የጥንቶቹ ክርስቲያኖች ዛሬ በፕሮቴስታንቶች ዘንድ እንደሚደረገው ቁርስ በልተው ሻይ ጠጥተው አረፋፍደው ሞቅ ሲልላቸው እሑድ ረፋዱ ላይ መጽሐፍ ቅዱስን በእጃቸው ይዘው ወደ "ጸሎት ቤት" እንደሚሄዱት ዓይነት አልነበሩም። እነዚያ ክርስቲያኖች መጽሐፍ ቅዱስ በየግላቸው ያልነበራቸው መሆኑ ብቻ ሳይሆን እንደ ዲድስቅልያ፣ ኖላዊ ዘሄርማስ፣ መልእክተ በርናባስ የመሳሰሉ መጻሕፍት እንደ ቅዱሳት መጻሕፍት ተቆጥረው በቤተ ክርስቲያን ተቀባይት ነበራቸው፣ ይነበቡና ትምህርት ይሰጥባቸውም ነበር።

የዚያን ዘመን ክርስቲያኖች ልክ ማርያም መግደላዊትና ሌሎቹም ቅዱሳት አንስት ወደ ጌታችን መቃብር የሄዱት እሑድ ማለዳ ላይ ገና ጨለማ ሳለ እንደ ነበረ ሁሉ፣ እነርሱም በጣም በጠዋት ገና ጨለማ ሳለ ወደ ቤተ ክርስቲያን ሄደው፣ ከዚያም ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ይነበብና በዚያ ቃል ላይ በቤተ ክርስቲያን አባቶች ትምህርት ይሰጥ ነበር። ዮሐ. 20፥1 ቀጥሎም ታላቅና ገናና ከሆነው ከምስጢረ ቁርባን ይሳተፋሉ። በመጨረሻም በኅብረት ማዕድ (ኢጋፔ) ተሳትፈው ይፈጽሙ ነበር።

በዘመነ ሐዋርያትና ከዚያም ቀጥሎ በነበሩት ዘመናት የነበሩ ክርስቲያኖችን፣ ነገረ ክርስትናን የሚያስተምሯቸውና በአጠቃላይ በሕይወታቸው ሁሉ የሚመሯቸው አባቶች ነበሯቸው። ዕብ. 13፥7፤ 17 እነዚያም መጀመሪያ ሐዋርያት ሲሆኑ ከዚያ ቀጥሎ ደግሞ የእነርሱ መንበር ወራሾች የሆኑና በሐዋርያዊ ቅብብሎሽ የተሾሙ ጳጳሳት ነበሩ። ሕዝበ ክርስቲያኑ የእግዚአብሔርን ቃል ይማሩ የነበረው ከአባቶች ነበር። ለሕዝቡ በቃል ትምህርትና በተግባራዊ ሕይወት የሐዋርያትን ትውፊት ያስተላልፉላቸው የነበሩትም እነዚያ አባቶች ነበሩ። 1 ቆሮ. 11፥2፤ 34 መጀመሪያ ላይ ሁሉም የክርስትና አስተምህሮ በቃል ብቻ ነበር። መጻሕፍት የተጻፉት ከዓመታት በኋላ ነበር። ቀኖናዊ የሆኑት ደግሞ ከዘመናት በኋላ ነበር። የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት መጻፋቸው የሐዋርያትን ትውፊት እንዲጠበቅና እንዲተላለፍ የተነገረውን (2 ተሰ. 2፥15) አስቀርቶታል ወይም ሽሮታል የሚልም አንድም ዐረፍተ ነገር የለም።

ንጹሕ ምንጭ ለነበሩት ለሐዋርያት ቅርብ የነበረውና ከእነርሱ እውነተኛውን አስተምህሮ የቀዳውና ከ120–202 ዓ. ም. የነበረው ቅዱስ ሄሬኔዎስ፣ ወንጌል እንዴት ይሰበክና ሰዎችም ያምኑ የነበረው እንዴት እንደ ነበር እንዲህ ሲል ጽፏል፦

. . . በክርስቶስ የሚያምኑ ብዙ ሕዝቦችና ወገኖች የሚቀበሉት ነገር ነው፤ እነርሱም ድኅነት በወረቀትና በቀለም ሳይሆን በልባቸው ውስጥ በመንፈስ ቅዱስ የተጻፈባቸው ናቸው። ስለዚህም ጥንታዊውን ሐዋርያዊ ትውፊት በጥንቃቄ ይጠብቃሉ፤ . . . **እነዚህም የተጻፈ መጽሐፍ በሌለበት በዚህ እምነት [በክርስትና] ያመኑ ናቸው**። እነርሱም ቋንቋንና ባህልን በተመለከተ ከእኛ የተለዩ ናቸው። በአስተምህሮ፣ በምግባር፣ በአጠቃላይ በሕይወታቸውና በአኗኗራቸው በተመለከተ ግን ከእምነታቸው የተነሣ ጠቢባን ናቸው፤ አነጋገራቸውን ሁሉ በእውነትና በጽድቅ፣ በንጽሕናና በጥበብ ሁሉ የሚያደርጉ በመሆናቸው እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኙ ናቸው።

ለእነዚህ ሰዎች የመናፍቃንን ፈጠራ ሄዶ ልሰብክላችሁ የሚላቸው ሰው ቢኖር፣ በራሳቸው ቋንቋ ቢናገራቸውና ሊሰብክላቸው ቢጀምር በአንድ ጊዜ ወዲያውኑ ጆሮዎቻቸውን እርሱን ከመስማት ይዘጋሉ፤ ጽርፈት የሆነውን ነገሩን ላለመስማት በሚችሉት ፍጥነት ቶሎ ብለው ከእርሱ ይሸሻሉ።[19] ስለዚህም የሐዋርያት ጥንታዊ ትውፊት ያላቸው ከመሆናቸው የተነሣ በእነዚህ መናፍቃን የሚነገረውን ነገር ወደ መስማት ሐሊናቸውን አያዘነብሉትም። (በእንተ ኑፋቄያት፣ መጽሐፍ 3፣ ምዕ. 4. ቁ. 2)

ለጥንቱ ክርስትና የዐይን ምስክር የሆነው ቅዱስ ሄሬኔዎስ እንደ ነገረን፣ ከባድና አስቸጋሪ በነበሩት በእነዚያ የመጀመሪያ ዘመናት ውስጥ ክርስትና የተስፋፋውና የተሰበከው በመጽሐፍ ላይ ተንጠልጥሎ ሳይሆን ሐዋርያዊው ትውፊት በቃል እየተሰበከ ነበር። ከሁለቱ በስተቀር (ከማቴዎስና ዮሐንስ) ሌሎቹ ሐዋርያት ወንጌልን አልጻፉም። ሆኖም ወንጌልን አልጻፉም ማለት ግን አልሰበኩም ማለት አይደለም።

ለምሳሌ ቅዱስ ቶማስ በሕንድ ወንጌልን መስበኩ የታወቀ ነው። ሆኖም ቅዱስ ቶማስ ወንጌል አልጻፈም። ሕንዶች ወንጌልን እንዴት ተማሩ? እንዲሁም በቅዱስ ቶማስ ዘመን ያልነበሩና ከእርሱ ዕረፍት በኋላ የተነሡ ሕንዳውያን ቅዱስ ቶማስ ያስተማረው ትምህርት ምን እንደሆነ በምን ማወቅ ቻሉ? ከቅዱስ ቶማስ የተማሩትንና የተቀበሉትን ትውፊት በመጠበቅ ነው! (2 ተሰ. 2፥15)። ታዲያ የሕንድ ክርስቲያኖች ቅዱስ ቶማስ መጽሐፍ ስላልጻፈ ክርስትናን አልተቀበሉም

[19](Those who, in the absence of written documents, have believed this faith, are barbarians, so far as regards our language; but as regards doctrine, manner, and tenor of life, they are, because of faith, very wise indeed; and they do please God, ordering their conversation in all righteousness, chastity, and wisdom. If any one were to preach to these men the inventions of the heretics, speaking to them in their own language, they would at once stop their ears, and flee as far off as possible, not enduring even to listen to the blasphemous address.)

ነበር ሊባል ነው? የማቴዎስና የማርቆስ፣ የሉቃስና የዮሐንስ ወንጌል ተጠቃልለው እስከሚደርሷቸው ድረስ ክርስቲያኖች አልነበሩም ሊባል ነው? እንደዚሁም የቅዱስ ጳውሎስና የሌሎቹም ሐዋርያት መልእክቶች ተሟልተው እስከሚደርሷቸው ድረስ ክርስቲያኖች አልነበሩም ማለት ነው? "አይ፤ ክርስቲያኖች ነበሩ" ካሉ፣ ታዲያ ያን ጊዜ የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ባይኖራቸውም የወንጌል ትምህርት በትውፊት የነበራቸው ከመሆኑ የተነሣ ክርስቲያኖች ከነበሩ ያን ክርስትናን ከመጀመሪያው ያገኙበትን መንገድ - ትውፊትን - በኋላ አታስፈልገንምና እንጣልህ የሚሉበት ምክንያት ምንድን ነው? እንደዚሁም መጻሕፍቱ ተሟልተው ሳይደርሷቸው በፊት ባላገኟቸው (እና ገና ባልተጻፉት) መጻሕፍት ውስጥ የነበረውን የክርስትና ትምህርት ከየት አገኙት? ያገኙት ከትውፊት መሆኑ ግልጽ ነው።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች ትምህርት እውነት ቢሆን ኖሮ፣ ቤተ ክርስቲያን የእግዚአብሔር ቃል ተጽፎ አልቆ እጇ ላይ ሳይኖራት የነበረችበት ዘመን ስለነበር (ቢያንስ ከ98 ዓ. ም. በፊት) ሁሉም የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ተጽፈው እስከሚያልቁ ድረስ ይነሡባት የነበሩ ጥያቄዎችንና የገጠሟትን ሃይማኖታዊ ጉዳዮች በሥልጣንና በእርግጠኝነት መወሰን አትችልም ነበር ማለት መሆኑ ነው! እነዚያ የመጀመሪያዎቹ የቤተ ክርስቲያን ዘመናት ከመቸውም ጊዜ በላይ እጅግ ከባዶች ነበሩ። ክርስትና ገና አንድ ተብሎ እየተሰበከ ስለነበር ከአይሁድና ከአሕዛብ ጋር የሞት የሽረት ተጋድሎ የሚደረግበት ዘመን ነበር።

በዚያን ዘመን ክርስትናን መስበክ ጥቅጥቅ ባለ ጫካ ውስጥ መንገድ እያወጡ እንደ መሄድ ነበር። አይሁድና አሕዛብ በሌላ ነገር ባይስማሙም ክርስቶስን ለመግደል ተስማምተው እንዳደረጉት ሁሉ አካሉን ቤተ ክርስቲያንን ለማሳደድም እንደዚያው ተደጋጋፊዎች ነበሩ። በዚያውም ላይ የተለያዩ ኑፋቄዎች እየገጠሟት ነበር። ገላ. 1፡6-9 የክርስቲያኖች ትምህርት ያለው በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ብቻ ከሆነ ያን ጊዜ መጽሐፍ ቅዱስ ሙሉ በሙሉ ተጽፎ ገና ስላላለቀ፣ ከክርስቶስ ዕርገት በኋላ እስከ 98 ዓመት የነበሩ የዚያን ዘመን ክርስቲያኖች (ከ34-98 ዓ. ም.) ነገረ ሃይማኖታዊ ጉዳዮችን የሚያስተምሩት በምን መሠረትነት ነበር? ክርክር ሲነሣባቸውስ የሚወስኑትና የሚዳኙት በምን ነበር?

መጽሐፍ ቅዱስ ከመጻፉ በፊት፣ ከዚያም በቀኖና ከመቀነኑ በፊት የነበሩት ሁሉም ክርስቲያኖች፣ ከዚያም ደግሞ የማተሚያ መሣሪያ ከመሠራቱ በፊት የነበሩት አብዛኞዎቹ ክርስቲያኖች አሁን በምናውቀው ዓይነት ሁኔታ መጽሐፍ ቅዱስ በእጃቸው አልነበራቸውም። ማንበብና መጻፍ የሚችሉትም በጣም ጥቂቶቹ ብቻ ነበሩ። ዛሬም ቢሆን በመላው የዓለማችን ክፍል ያሉት ሰዎች ሁሉም አይጽፉም አያነቡም። የማተሚያ መሣሪያ ከመሠራቱ በፊት ሙሉውን መጽሐፍ ቅዱስ

ለማስጸፍ የሚችሉት በጣም ጥቂት ሰዎች ብቻ ነበሩ። ክርስትና "መጽሐፍ ቅዱስና መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ነው" የሚለው አስተምህሮ መጽሐፍ ቅዱስን በቀላሉ ለማግኘት ሁኔታዎች ከመመቻቸታቸውና ከአካዴሚያዊ ትምህርት መስፋፋት ጋር ማንበብ የሚችለው ሰው መጠን ከመጨመሩ ጋር ተያይዞ የመጣ ከሀብትና ከኑሮ መመቻቸት አንጻር የተፈጠረ የምዕራባውያን ጽንሰ ሐሳብ ነው እንጂ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ከነበረው ነባራዊ ሁኔታና እውነታ ጋር ፈጽሞ የማይሄድ ነው። እንደዚህ የሚሉት ብዙዎቹ ፕሮቴስታንቶች ለብዙ ክፍለ ዘመናት መጽሐፍ ቅዱስ በተራው ሕዝብ እጅ ያልነበረ መሆኑን ካለማወቃቸውና ስለ ክርስትና ታሪካዊ እውነታ ምንም ግንዛቤ የሌላቸው ከመሆናቸው የተነሣ ነው። በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን በቋንቋቸው የተተረጎመ መጽሐፍ ቅዱስ ሳይኖራቸውና ከቃል ትውፊት እንጂ ከተጻፈ መጽሐፍ ቅዱስ ሳይማሩ ክርስትናን የተቀበሉ ብዙ አገሮችና ሕዝቦች ነበሩ።[20]

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ትክክል ቢሆን ኖሮ፣ በዘመነ ሐዋርያትና ከእነርሱ ቀጥሎ በነበሩት ዘመናት የነበሩት ክርስቲያኖች የእግዚአብሔር ቃል አልነበራቸውም ማለት ነው። በዚያ ዘመን መጽሐፍ ቅዱስን ወደ መጻሕፍት መሸጫ ሱቆች ሄዶ መግዛት የሚቻልበት ሁኔታ አልነበረም፣ እንደዛሬው የማተሚያ መሣሪያ ስላልነበረ መጻሕፍት የሚጻፉት በእጅ እየተገለበጡ ነበርና። የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ሁሉም አንድ ላይ ተጠቃልለው በእያንዳንዱ ክርስቲያን ቤት የሚገኙበት ሁኔታ አልነበረም። እንኳን በእያንዳንዱ ግለሰብ እጅ ሙሉ መጽሐፍ ቅዱስ ሊገኝ ይቅርና የተወሰኑ መጻሕፍት ከተገኙም እንኳ ትልቅ ነገር ነበር። ታዲያ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሯቸው እንደሚለው እያንዳንዱ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን በራሱ አንብቦ የመጽሐፉን ቃል ከመጽሐፉ ቃል ጋር እያገናዘበ እንዲተረጉምና በራሱ አረዳድ እንዲሄድ የሚባል ከሆነ፣ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት እንኳን በቀኖና ሊወሰኑ ገና ተጽፈው እንኳ ባላለቁበት ዘመን የነበሩ ክርስቲያኖች ዘመን ይህ አስተምህሮ እንዴት ሊሠራ ይችል ነበር?

4. **ጌታችን የሰጠን ትምህርት እና ሕይወት በምልዓት ያለው በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ነው።**

ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ የሰጠን ትምህርትና የሕይወት ምስጢራት በምልዓት ያሉት በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ነው። በመጽሐፍ የተጻፈው ሊጻፍና ሊገለጽ የሚቻለው ያህል ብቻ ነው። ሊገለጽ የሚቻለው ያህል ብቻ ሳይሆን በጽሑፍ ሊገለጽ የሚገባውን ያህል ነው። ለምሳሌ ጌታችን ስለ ጥምቀት "ሰው ከውኃና ከመንፈስ ካልተወለደ በቀር ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ሊገባ አይችልም" ብሎ አስተምሯል።

[20] P.E. Hallett, *A Catholic Dictionary*, 1951, p 782.

ዮሐ. 3፥5 እንደዚሁም "ሥጋዬን የሚበላ ደሜንም የሚጠጣ የዘላለም ሕይወት አለው" ብሎ አስተምሯል። ዮሐ. 6፥54-55 በጸሎተ ሐሙስ ደግሞ ይህን ምስጢር በተግባር ፈጽሞ ለደቀ መዛሙርቱ አሳይቷቸዋል። በመጽሐፍ የተጻፈው ይኸው ነው! ግን የእነዚህ ምስጢራት አፈጻጸም ተግባራዊ ክዋኔና ሕይወት ያለው በቤተ ክርስቲያን ነው። ከቤተ ክርስቲያን ውጭ እነዚህን ሕይወታዊ ምስጢራት ማግኘትና መረዳት አይቻልም።

ለምን? ቢባል እነዚህ አምላካዊ ምስጢራት ሙሉ በሙሉ በቃላትና በዐረፍተ ነገሮች ብቻ ተከናውነው ሊገለጹና ሊብራሩ ስለማይችሉ ነው። ሐዋርያው ቅዱስ ጳውሎስ ለቆሮንቶስ ክርስቲያኖች ምስጢረ ቁርባንን በተመለከተ ሊያደርጉ ስለሚገባቸው ታላቅ ጥንቃቄ በመልእክቱ ላይ የተወሰነ ነገር ከጻፈላቸው በኋላ **"የቀረውንም ነገር በመጣሁ ጊዜ እደነግጋለሁ"** ያለው ለዚህ ነው። 1 ቆሮ. 11፥34 አዎ፥ ታላቅና ገናና ስለሆነው ምስጢረ ቁርባን በመልእክት ብቻ ተንትኖ መጻፍ አይቻልምና። ስለሆነም ቅዱስ ጳውሎስ ይህን ምስጢር በተመለከተ ያሉ ተግባራዊ ሁኔታዎችን ራሱ በአካል በሄደ ጊዜ ደነገገላቸው። **"የቀረውንም ነገር በመጣሁ ጊዜ እደነግጋለሁ"** ያላቸውን እነዚያን ድንጋጌዎቹን በየትኛውም መልእክቶቹ ላይ ጽፏቸው አናገኛቸውም። በሌላ መልእክቱ ላይ ስለ ቅዱስ ቁርባን አንሥቶ አልተናገረም። ይህም ማለት እነዚያን በአካል ሄዶ ለቆሮንቶስ ክርስቲያኖች የደነገገላቸውን ነገሮች በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ባለ ሕይወታዊ የተግባር ክዋኔና ቅብብሎሽ (በትውፊት) እንጂ በመጽሐፍ ቅዱስ በጥቁርና በነጭ ተጽፈው አናገኛቸውም ማለት ነው።

ከቤተ ክርስቲያን ሕይወት ወጥተው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚል የስህተት ትምህርት ፈጥረው የሚጓዙ ወገኖቻችን ያጡትም ይኸን ሕይወት ነው። ለምሳሌ የከበረ ማዕድን ወዳለበት አንድ ቦታ የሚያመለክትን ካርታና ስለዚያ የሚናገር ጽሑፍን ይዞ ያን ሌሊትና ቀን እያጠና ያለ ሰው፥ ማዕድኑ ወዳለበት ቦታ ሄዶ ማዕድኑን አውጥቶ ከማዕድኑ ከሚገኘው ጥቅም ካልተሳተፈ ካርታውንና መጽሐፉን ማጥናቱ ብቻ ጥቅሙ ምንድን ነው? የእግዚአብሔር ቃል በራሱ ሕይወት መሆኑ እንዳለ ሆኖ፥ ከዚህም ጋር ደግሞ ጸጋውን እናገኝ ዘንድ የሚመራ ካርታ ስለሆነ ያ ጸጋው ደግሞ የሚገኘው በራሱ በመጽሐፉ ውስጥ ሳይሆን በቅድስት ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ስለሆነ፥ ከቤተ ክርስቲያን ውጭ ሆኖ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" እያሉ መሟገት ከንቱ ድካም ብቻ ነው! ለምሳሌ መጽሐፍ ቅዱስ ስለ ጥምቀት አስፈላጊነትና በጥምቀት ስለሚገኘው ጥቅም ይነግረናል እንጂ ጥምቀት መጽሐፍ ቅዱስን በማንበብ ብቻ አይገኝም። ራሱ መጽሐፉም ጥምቀት አይደለም። መጽሐፍ ቅዱስ ስለ ቅዱስ ቁርባን ይነግረናል እንጂ ራሱ መጽሐፉ የኢየሱስ ክርስቶስ ቅዱስ ሥጋና ደም አይደለም። እነዚህ የሕይወት ምስጢራት በተግባር የሚገኙት በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ብቻ ነው።

ከዚሁም ጋር እውነተኛውን የእግዚአብሔርን መገለጥ የተቀበለችው ሕያዊት የሆነችው ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ሳትሆን በመጽሐፍ ላይ የተጻፈው ጽሑፍ ነው (መጽሐፉ ነው) ማለት ከክርስትና የእግዚአብሔር የመገለጥ አስተምህሮ ይልቅ ሙስሊሞች ስለ መገለጥና ስለ ቁርዓን ወደሚሉት ነገር የቀረበ እሳቤ ነው። እንዲሁም ይህ መጽሐፍን የማምለክ ዝንባሌ (Biblical Fundamentalism) ወይም መጽሐፍ ቅዱስ አምላኪ (Bible worshiper) መሆን ነው። ቅዱስ ጳውሎስ "የእውነት ዐምድ" ያላት ቤተ ክርስቲያንን ነው፤ ምክንያቱም እውነት የሚጠበቀው ያን እውነት በሚረዳና በሚተረጉም ሕይወት ባለው አካል እንጂ እንዲሁ በብራናና በወረቀት ላይ በተጻፈ ነገር ላይ ብቻ አይደለምና። ቅድስት ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን እየጠቀሱ ባእድ ትምህርት የሚያስተምሩና ከእምነቷ የሚቃረኑ መናፍቃን ሲነሱባት ስታወግዝና ስትለይ፤ እውነቱንም ስትጠብቅ የኖረችው እውነተኛው አረዳድ በእርሷ ዘንድ ስላለ ነውና። ጌታችን ቤተ ክርስቲያንን የማይሰማ ሰው ቢኖር እርሱን እንደ ኢአማኒ ቁጠሩት ያለውም ለዚህ ነው። ማቴ. 18፡17

መጽሐፍ ቅዱስ ከመጻሕፍት መሸጫ ሱቆች ገዝተን በፈለግነው መንገድ ልንረዳውና ልንተረጉመው የተጻፈ መጽሐፍ ሳይሆን እግዚአብሔር በልጁ ሰው መሆን የገለጠውን እውነትና ሕይወት የያዘችው ቤተ ክርስቲያን ይህን ሕይወትና እውነት ማስተማሪያና መጠበቂያ ይሆናት ዘንድ የጻፈችውና የጠበቀችው ነው። ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስ መላውን የእግዚአብሔር የመገለጥና የመዳን ምስጢር ከያዘችው ከቤተ ክርስቲያን ውጭ ሊተረጎም አይችልም፤ ከመጀመሪያው አንሥቶ እንደዚያ አልነበረምና።

5. **እግዚአብሔር ሰውን ያስተማረውና የሚያስተምረው በመጽሐፍ ብቻ አይደለም።**

እግዚአብሔር ከጥንት ከመጀመሪያው ለሰው ልጆች ራሱን የገለጠውና ያስተማረው "በመጽሐፍ ብቻ" አልነበረም። እግዚአብሔር ከአዳም ጋር ከውድቀት በፊትም ሆነ በኋላ ይነጋገር የነበረው በመጽሐፍ አልነበረም። ከዚያም በኋላ ከአቤል ጋር፤ ከሄኖክ ጋር፤ ከኖኅ ጋር፤ ከአብርሃም ጋር፤ ከይስሐቅ ጋር፤ ከያዕቆብ ጋር ሲነጋገር የነበረው ቃሉን በመጽሐፍ አስጽፎ እየሰጣቸው አልነበረም። እግዚአብሔር ለሰዎች ሕጉን በመጽሐፍ አስጽፎ የሰጣቸው ከአዳም በኋላ ከሦስት ሺህ ዓመታት በላይ ቆይቶ ነበር።

እግዚአብሔር ለሰው ልጅ የመጀመሪያ አስተማሪ አድርጎ የሰጠው በብራና ወይም በወረቀት ላይ የተጻፈ መጽሐፍን ሳይሆን ሥነ ፍጥረትን ነበር። በዳዊት መዝሙር ላይ እንዲህ ተብሎ እንደ ተጻፈ፡-

ሰማያት የእግዚአብሔርን ክብር ይናገራሉ፤ የሰማይም ጠፈር የእጁን ሥራ ያወራል።

ቀን ለቀን ነገርን ታወጣለች፤ ሌሊትም ለሌሊት እውቀትን ትናገራለች።

ነገር የለም መናገርም የለም፤ ድምፃቸውም አይሰማም።

ድምፃቸው ወደ ምድር ሁሉ፤ ቃላቸውም እስከ ዓለም ዳርቻ ወጣ። መዝ. 18፡1-4

ቸር የሆነ እግዚአብሔር የሰውን ልጅ ለብዙ ዘመናት በቀለምና በብራና ላይ በተጻፈ መጽሐፍ ሳይሆን ሥነ ፍጥረቱን መማሪያ መጽሐፍ አድርጎ የሰጠው ለዚህ ነው። ምክንያቱም ከጥንቱ ቃሉን በቀለምና በብራና ላይ በፊደላት ቅንብር በተጻፈ መጽሐፍ ጽፎ ቢሰጥ ኖሮ ማንበብ ከሚችሉ በጣም ጥቂት ሰዎች በስተቀር ሌላው ሕዝብ ሊማርበት አይችልም ነበር። አንድ መጽሐፍ ለመጻፍ የብዙ እንስሳት ቆዳ ያስፈልግ በነበረበት ዘመን ከጥቂት ባለጸጋዎች በስተቀር ተራው ሕዝብ መጽሐፍ ለማስጻፍ አቅም ስለማይኖረው እግዚአብሔርን ለማወቅ ዕድል አይኖረውም ነበር። እንደዚሁም መጽሐፍ ያላቸው ሰዎች እንኳ ቢኖሩ መጽሐፉ ክብደት ያለው ከመሆኑ የተነሣ ከቦታ ቦታ ሲንቀሳቀሱ ለመሸከምና ይዘው ለመጓዝ ይቸገሩ ነበር። ከዚህም የተነሣ የገንዘብ ዓቅም ለነበራቸው ሰዎች እንኳ ጠቀሜታው የተገደበ ይሆን ነበር።

እግዚአብሔር መጀመሪያ ለሰዎች ማስተማሪያ ባደረገው በሥነ ፍጥረት መጽሐፍነት ዘንድ ግን ይህ ሁሉ የለበትም። ከሥነ ፍጥረት አስተማሪነት የሚገኘው ትምህርት በባቢሎን የተፈጠረው የቋንቋ መደበላለቅ የማያግደው፣ ፊደል ማንበብ መቻል አለመቻል ልዩነት የማይፈጥርበት፣ ተደራሽነቱ በድሀና በሀብታም መካከል አንዳችም ልዩነት የሌለበት፣ ተሸከሙኝ ሳይል በሄዱበት ሁሉ የሚከተልና የሚገኝ፣ ሃያ አራት ሰዓት የማይታጠፍና ሁል ጊዜም ዝግጁ የሆነ፣ ለሰው ልጅ ሁሉ የተሰጠ መማሪያ "መጽሐፍ" ነው። እንደዚያ ባይሆን ኖሮ እግዚአብሔር ለሀብታሞች ወይም ለተማሩ ሰዎች ወይም ቋንቋቸው የጽሑፍ ፊደል ላለው ሕዝቦች ብቻ እርሱን የሚያውቁበት ዕድል ሲሰጣቸው ለሌላው ለአብዛኛው ግን ይህን ዕድል የነፈገ በሆነ ነበር። በዚህም ሲፈርድ በእኩል እየፈረደ እርሱን ለማሳወቅ የሰጠው ዕድል ግን እኩል አይደለም ሊባል ይችል ነበርና። ሆኖም ቸር የሆነው እግዚአብሔር ግን እንደዚያ አላደረገም።

እግዚአብሔር ስለ እርሱ ልናውቀው የሚገባውን እውቀት በሥነ ፍጥረት አማካይነት የገለጠ ስለሆነና ከሥነ ፍጥረት መምህርነት ተምሮ እግዚአብሔርን ማወቅ የማይችል አንድም ሰው የሌለ በመሆኑ፣ ማንም ሰው እግዚአብሔርን ላለማወቁና ላለማምለኩ የሚያስተምረኝ በማጣቴ ነው ብሎ ሊያመካኝ አይችልም። ቅዱስ ጳውሎስ በሮሜ መልእክቱ ላይ እንደዚህ ያለው ይህን ሲያስረዳ ነው፡-

የማይታየው ባሕርይ፣ እርሱም የዘላለም ኃይሉ፣ ደግሞም <u>አምላክነቱ ከዓለም ፍጥረት ጀምሮ ከተሠሩት ታውቆ ግልጥ ሆኖ ይታያልና፤</u> <u>ስለዚህም</u> <u>እግዚአብሔርን እያወቁ እንደ እግዚአብሔርነቱ መጠን ስላላከበሩትና ስላላመሰገኑት የሚያመካኙት አጡ፤</u> . . . ሮሜ 1፡20-21

ገና ወንጌል ከመስበኩ በፊት ስለነበሩ አሕዛብ ሲናገር "እግዚአብሔርን እያወቁ እንደ እግዚአብሔርነቱ መጠን ስላላከበሩትና ስላላመሰገኑት የሚያመካኙት አጡ" ያለው ወደ አሕዛብ ዘንድ ተልኮ ሄዶ ስለ እግዚአብሔር ያስተማራቸው ሐዋርያ ወይም ነቢይ ስለነበረ አይደለም። ከሥነ ፍጥረት መምህርነት ሊማሩ የሚችሉ ሆነው ሳለ እነርሱ ግን ከዚያ ይልቅ ራሱን ፍጥረቱን ወደ ማምለክ መሄዳቸውን በማውሳት ስንፍናቸው ምክንያት የሌለው መሆኑን በመግለጥ በብርቱ ወቀሳቸው እንጂ። እንዲሁም "ከጥንት ጀምሮ እግዚአብሔር <u>**በብዙ ዓይነትና በብዙ ጎዳና** ለአባቶቻችን በነቢያት **ተናገረ**</u>" አለ እንጂ "በመጽሐፍ ብቻ ተናገረን" አላለም።፡ ዕብ. 1፡1-2

እንዲሁም "ይነግራ ሰማያት ጽድቀ ዚአሁ ወኩሎሙ አሕዛብ ርእዩ ስብሐቲሁ - ሰማያት የእርሱን ጽድቅ አወሩ፣ አሕዛብም ሁሉ ክብሩን አዩ" ተብሏል። መዝ. 96፡6 ጠቢቡ ሰሎሞንም ሰዎች ጉንዳንን አይተው ይማሩ ዘንድ ተናግሯል። ምሳ. 6፡6 ጌታችንም የምድረ በዳ አበቦችንና የሰማይ ወፎችን እንማርባቸው ዘንድ ተናግሯል። ማቴ. 6:28-30 ፤ ሉቃ. 12:27-28 ስለሆነም እግዚአብሔር የሚያስተምረው በመጽሐፍ ብቻ ነው ማለት ራሱን መጽሐፍ ቅዱስን መቃወም ነው።

እግዚአብሔር ሕጉን ለሰዎች በመጽሐፍ አስጽፎ የሰጠው ከአዳም በኋላ ሦስት ሺህ በላይ ዓመታትን ዘግይቶ ማድረጉ ያለ ምክንያት ያደረገው ይመስለናልን? እግዚአብሔር ገና ከጥንቱ መጽሐፍ ጽፎ ቢሰጠን ኖሮ፣ እንደ ሉተራውያንና መሰሎቻቸው ያሉ "መጽሐፍ አምላኪዎች" ((Bible worshipers) የሆኑ አካላት "መጽሐፍ ብቻ" እያሉ እንዳያውኩ አርቆ ለማጠር አይሆን ይሆን? ምክንያቱም የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት በብሉይ ኪዳን ዘመን ከብዙ ሺህ ዓመታት በኋላ፣ በሐዲስ ኪዳን ደግሞ ከጌታችን ትንሣኤና ዕርገት ከብዙ ዓመታት በኋላ የተጻፉ ሆነው ሳለ፣ ለመሰባሰብና አንድ ለመሆን ደግሞ ሌላ ረጅም ዘመናትንና ውጣ ውረዶችን ያለፉ ሆነው እያለ እንኳ፣ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" እያሉ የሚሳሳቱ ከሆነ፣ ከመጀመሪያው ጀምሮ እንደዚህ ባይሆን ኖሮማ ምናልባት ለስህተታቸው ሰፊ መንገድ ባገኙ ነበር!

በሐዲስ ኪዳን ዘመንም መጽሐፍ ቅዱስ በእያንዳንዱ ክርስቲያን እጅ ሊኖረው የቻለው በ15ኛው መቶ ዓመት ጆን ጉተንበርግ በተባለ ጀርመናዊ የማተሚያ

መሣሪያ ከተሠራ በኋላ ነበር። ከዚያ በፊት በነበሩት 1,400 ዓመታት ከላይ እንደ ተገለጸው ለጥቂት ባለጸጋዎች ብቻ ካልሆነ በስተቀር መጽሐፍ ቅዱስ በሁሉም ሰው እጅ አልነበረም። ከማተሚያ መሣሪያ መሠራት በኋላም[21] ቢሆን መጽሐፍ ቅዱስን በአንድ ላይ ጠርዞ በብዙ ቁጥር ለማተም እንደገና ሌሎች ጊዜያትን ወስዷል። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው አስተምህሮ መሠረት ክርስቲያኖች ስለ ክርስትና የሚያውቁት መጽሐፍ ቅዱስን ራሳቸው ለራሳቸው አንብበውና ተርጉመው ብቻ ነው የሚል ስለሆነ፣ ይህ እንዲሆን ደግሞ እያንዳንዱ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስ በእጁ ላይ የነበረው ወይም ለማንበብ ዕድል የነበረው ይሆን ዘንድ የግድ ይላል። ሆኖም ነገሩ ግን እንደዚያ አልነበረም።

እዚህ ላይ ዋናው ነጥብ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች የፈጠራ ትምህርት ከእግዚአብሔር አምላካዊ መግቦትና አሠራር ጋር ተቃራኒ መሆኑ ነው። ይህም ማለት እግዚአብሔር በአካላዊ ቃል ሰው መሆን ራሱን ከገለጠ በኋላ፣ እንደገና መልሶ ይህን እውነታ ለሰው ልጆች ሙሉ ሆኖ የሚገለጥበትንና የሚታወቅበትን መንገድ (መጽሐፍ ቅዱስን) ሳይሰጥ እንደገና ለ1,500 ዓመታት አዘግይቶባቸዋል ማለት ነው። ይህ ከሆነ ደግሞ እግዚአብሔርን ጨካኝና ንፉግ ያሰኘዋል እንጂ ቸርና ደግ የሚያሰኘው አይሆንም።

ሆኖም እግዚአብሔር ግን እንዲህ አይደለም፣ በጭራሽ! እግዚአብሔር በአንድያ ልጁ ሰው መሆን ራሱን እንደ ገለጠልን፣ አካላዊ ቃሉም "እውነትና ሕይወት እኔ ነኝ" እያለ እንዳስተማረን፣ ይህን እውነትና ሕይወት ታስተምርና ትጠብቅ ዘንድ አካሉ የሆነች ቤተ ክርስቲያንን መሥርቶ ሰጠን እንጂ የማተሚያ መሣሪያ እስከሚሠራ ድረስ ለብዙ መቶ ዓመታት ሰዎች ከእውነቱና ከጸጋው ቃል ርቀው እንዲባዝኑ አልተዋቸውም።

በአንደኛው፣ በሁለተኛው፣ በሦስተኛው፣ . . . መቶ ዓመት የነበሩ ክርስቲያኖች ስለ ክርስቶስ እየመሰከሩ በፍቅሩ እየተናደዱ ወደ እሳት ሲጣሉና በሠይፍ ሲገደሉ ጸንተው የኖሩት ፕሮቴስታንቶች እንደሚሉት መጽሐፍ ቅዱስ በአንድ ላይ በጥራዝ ኖሯቸው አልነበረም፣ የቃሉ ባለቤት ከሆነችው ከቅድስት ቤተ ክርስቲያን ቃሉን በሥርዐተ አምልኮና በስብከት ይማሩትና በምስጢራት ይኖሩት ስለነበር ነው እንጂ፣ ብዙ ቅዱሳን ባሕታውያንም መጽሐፍ የሚባል ነገር በእጃቸው ሳይኖራቸው ስለ

[21] በ 1455 ዓ. ም. ገ. የማተሚያ መሣሪያን የፈለሰፈው ዮሐንስ ጉተንበርግ እምነቱ ካቶሊክ ነበር። በሠራው መሣሪያ ለመጀመሪያ ጊዜ ያተመው መጽሐፍም **መጽሐፍ ቅዱስ** ነበር። ያተመው መጽሐፍ ቅዱስ የያዛቸው መጻሕፍት ብዛትም 73 ነበር (66 አልነበረም)። በኋላ ላይ ፕሮቴስታንቶች ከብሉይ ኪዳን መጻሕፍት 7 መጻሕፍትን ቀነሱ እንጂ ከዚያ በፊት 66 የሚባል የታተመም የዓለም አብያተ ክርስቲያን የተስማሙበትም የለም።

እግዚአብሔር ፍቅር ሲሉ "ከኃጢአት ጋር ደምን እስከ ማፍሰስ ድረስ" ተጋድለዋል። ዕብ. 12፡4 እውነተኛ ፍቅራቸውን በቃልና በወሬ ሳይሆን በተግባር ገልጠዋል።

ስለዚህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ እግዚአብሔር ከጥንት ጀምሮ ሕዝቡን ሲያስተምርበትና ሲገለጥበት ከኖረው መንገድ ጋር ተቃራኒ ነው። ከዚህም ጋር እግዚአብሔርን ለመጽሐፍ ተገዥ የሚያደርግና አሠራሩን ሁሉ የግድ በተጻፈው መንገድ ብቻ ማድረግ አለበት የሚል ገዳቢ የሆነ ሰው ሠራሽ ሥርዓት ነው።

እግዚአብሔር የተጻፈውን ቃሉን በአግባቡ ተጠቅመን በቅድስት ቤተ ክርስቲያን ያስቀመጠውን የመዳን ጸጋ ተቀብለን ከእርሱ ጋር በሕይወት እንኖር ዘንድ መጻሕፍትን ቢሰጠን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ወደሚል መጽሐፍ አምላኪነት መሄድ፣ ሥራውን አይተን ሠሪውን እናውቅበትና እናመሰግንበት ዘንድ ውብና ድንቅ የሆነ ሥነ ፍጥረትን ቢሰጥ፣ ራሱን ፍጥረቱን እያመለኩ ወደ እግዚአብሔር ሳይደርሱ እንደ ቀሩ እንደ አሕዛብ መሆን ነው። እግዚአብሔር የፈጠረው ነገር ሁሉ መልካም ነው፣ ሆኖም አጠቃቀሙን ካላወቁበት ግን ይጎዳል፤ ጉዳቱ ግን የስጦታው ችግር ሳይሆን ስጦታውን የሚጠቀመው ሰው አጠቃቀም አለማወቅ የሚያመጣው ችግር ነው። የሕይወት መሪ ሆኖ የተሰጠንን መጽሐፍ ቅዱስ በአግባቡ በመጠቀም ፋንታ፣ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚል መጽሐፍን የማምለክ ራስ ፈጠር "ጣዖታዊነት" ውስጥ ወድቀው የሕይወት ቃል በሆነው መጽሐፍ ቅዱስ የተጎዱና እየተጎዱ ያሉት የዚህ ተጠቂዎች ናቸው!

6. **"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚል አስተምህሮ ከ14ኛው መቶ ዓመት በፊት** አልነበረም።

ይህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች ዋና መሠረተ እምነት የሆነው አስተምህሮ እስከ 14ኛው መቶ ዓመት ድረስ በቤተ ክርስቲያን ዘንድ ተሰምቶ የሚያውቅ ነገር አልነበረም። ይህም ይህ ትምህርት ከጌታና ከሐዋርያቱ ትምህርት እጅግ የራቀና የወጣ መሆኑን በራሱ ይናገራል። ምክንያቱም ከሐዋርያት ቀጥሎ ከነበሩት አባቶች አንሥቶ እስከ አራተኛውና አምስተኛው መቶ ዓመት ከነበሩት ቀደምት የቤተ ክርስቲያን አባቶች መካከል "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ብሎ ያስተማረ የቤተ ክርስቲያን አባት የለም። ፕሮቴስታንቶች ይህን መሠረታዊና ያፈጠጠ እውነታ ሸፋፍነው ሊያልፉት ወይም ችላ ሊሉት ይሞክራሉ። ሆኖም ይህ ነጥብ ብቻ በራሱ ይህን አስተምህሮ ውድቅ ሊያደርገው የሚችል ነው። ምክንያቱም ኑፋቄ ማለት በቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ ያልነበረ እንግዳ ነገር እንደ መሆኑ፣ ይህ ሉተር ወለድ የኑፋቄ አስተምህሮም በቤተ ክርስቲያን ሕይወት ውስጥ ለ1,400

ዓመታት ያልነበረ አዲስ የፈጠራ እምነትና እንግዳ ትምህርት ነውና። ሉተር ከአምስቱ ብቻዎች አንዱና ዋናው አድርጎ ከማቅረቡ በፊት፣ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ስለሚል ጉዳይ የቤተ ክርስቲያን ታሪክ የሚናገረው አንድም ነገር የለም።

ፕሮቴስታንቶች ይህን አጣብቂኝ፣ "ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ 'መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ' ብሎ ስለሚያስተምር ይህ አስተምህሮ ከጌታችን የተገኘ ነው" በማለት ለማለፍ ይሞክራሉ። ሆኖም ከላይ እንዳየነው መጽሐፍ ቅዱስ እንዲህ ያለ ነገር አንድም ቦታ አይናገርም። ፈጽሞ! በሐዋርያት ዘመን ቅዱስ ጳውሎስ ወንጌልን እያስተማረ ሳለ ቢጽ ሐሳውያን የተባሉ ወገኖች "እንደ ሙሴ ሥርዓት ካልተገረዛችሁ ትድኑ ዘንድ አትችሉም ብለው ወንድሞችን ያስተምሩ ነበር" ተብሎ እንደ ተጻፈው፣ የስህተት ትምህርት እያስተማሩ በክርስቲያኖች መካከል ውዝግብ እየፈጠሩ ለሐዋርያዊ ተልእኮው መሰናክል ሆኑበት። የሐዋ. 15፡1 ያን ጊዜ ቅዱስ ጳውሎስ በጉዳዩ ላይ ራሱ ውሳኔ አልሰጠም። ጉዳዩ በኢየሩሳሌም በሐዋርያት ጉባኤ ይወሰን ዘንድ የተመረጡ ሰዎች እንዲሄዱ ተደረገ እንጂ፣

> . . . ስለዚህ ክርክር ጳውሎስና በርናባስ ከእነርሱም አንዳንዶች ሌሎች ሰዎች ወደ ሐዋርያት ወደ ሽማግሌዎችም ወደ ኢየሩሳሌም ይወጡ ዘንድ ተቈረጠ። . . . ሐዋርያትና ሽማግሌዎችም ስለዚህ ነገር ለመማከር ተሰበሰቡ። የሐዋ. 15፡2-6

ቅዱሳን ሐዋርያት ይህን ሃይማኖታዊ ጉዳይ በጉባኤ ተሰብስበው ከመከሩ በኋላ እንዲህ የሚል ውሳኔ ወሰኑ፡-

> ለጣዖት ከተሠዋ፣ ከደምም፣ ከታነቀም፣ ከዝሙትም ትርቁ ዘንድ ከዚህ ከሚያስፈልገው በቀር ሌላ ሸክም እንዳንጭንባችሁ እኛና መንፈስ ቅዱስ ፈቅደናል። የሐዋ. 15፡28

የቅዱስ ጳውሎስ ትምህርት ትክክል ነበር፣ በሐዋርያት ጉባኤ የተወሰነውም እርሱ ያስተማረው ትምህርት ነበር። እርሱን ተቃውመው ሲያስተምሩ የነበሩት ሰዎች ትምህርታቸው ስህተት መሆኑ በጉባኤው ተመስክሯል። ነገሩ እንደዚያ ቢሆንም ግን ቅዱስ ጳውሎስ ብቻውን በራሱ አልወሰነም። ታዲያ ቅዱስ ጳውሎስ እንኳ በጉባኤ ላይ የተወሰነውን እንጂ በራሱ በግሉ የነበረውን አስተምህሮ ይዞ እኔ እንደ ገባኝና እንደ ተረዳሁት በራሴ መንገድ እመራለሁ ያለ ካልሆነ፣ የራሱን ግላዊ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል አረዳድ እንደ መጨረሻ እውነት አደርጋለሁ ለማለት የሚደፍር ማን ነው? ሌሎቹ ቅዱሳን ሐዋርያትም በክርስትና አስተምህሮ ላይ በተነሣው በዚህ ክርክር ወቅት እያንዳንዱ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን በግሉ እንዲያነብና ትክክል የሆነውን ነገር ለራሱ እንዲወስን ወደየቤቱ አላሰናበቱትም። የሐዋ. 15፡6-29

ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስን እያንዳንዱ ሰው በራሱና በመሰለው ሊተረጉም አይችልም፤ አይገባምም። ምክንያቱም ቤተ ክርስቲያን ጉባኤያዊት ናት እንጂ ግላዊት አይደለችም። ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስን አንተ በገባህ መንገድ ተረዳው፤ ስለ ክርስትና ለማወቅ በራስህ ማንበብና መተርጎም ትችላለህ" የሚለው ፕሮቴስታንታዊ ትምህርት በመጽሐፍ ቅዱስና በአባቶቻችን ትምህርትና ሕይወት ሲመዘን በተቃርኖ የቆመ ነው። የቤሪያ ሰዎችንም ቅዱስ ጳውሎስ ወደየቤታቸው እንዲሄዱና እርሱ የሚያስተምረው ትክክል መሆን አለመሆኑን በየግላቸው ለራሳቸው እንዲወስኑ አላላቸውም። የቤሪያ ሰዎች የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትን እርሱ ራሱ ቅዱስ ጳውሎስ ባለበት በየቀኑ እንዲያነቡና መሢሑን በተመለከተ ያስተማራቸው ትምህርት በብሉይ ኪዳን ከተነገረው ጋር የሚስማማና እውነት መሆኑን እንዲመረምሩ አደረጋቸው እንጂ። የሐዋ. 17፡10-12

በ50 ዓ. ም ገደማ ከተካሄደው የመጀመሪያው የሐዋርያት ሲኖዶስ ጀምሮ በዓለም አቀፍ ደረጃ በተካሄዱ የቤተ ክርስቲያን ጉባኤያት ውስጥ በአንዱም "በመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ እናምናለን" የሚል አንቀጽ አልተካተተም፤ "የሐዋርያት ጉባኤ (ሐዋርያዊት) በሆነች በአንዲት ቅድስት ኩላዊት ቤተ ክርስቲያን እናምናለን" አሉ እንጂ "በመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" እናምናለን አላሉም። ከዚህም ጋር በሐዋርያዊ ቅብብሎሽ መሠረት ከሐዋርያት መንበር ጋር ግንኙነት ያላቸውና ጥንታውያን የሆኑ አብያተ ክርስቲያን - ምሥራቅ ኦርቶዶክስ እና የሮማ ካቶሊክ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሮ አይቀበሉትም። ስለዚህ ይህ አስተምህሮ ለ1,500 ዓመታት ያልነበረና ሰው ሠራሽ የሰዎች ፈጠራ ነው ማለት ነው።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ በቀደምት ክርስቲያኖች የማይታወቅና ቀደምት አባቶችም ያላስተማሩት ስለመሆኑ፣ ፕሮቴስታንት ከሆኑ ምሁራን ውስጥም እውነቱን የመሰከሩ አሉ። ከእነዚህ መካከል የተወሰኑት ያሉትን ቀጥሎ እንመልከት።

ሮበርት ፕሬየስ (Robert Preus) የተባለው ፕሮቴስታንት ምሁር እንዲህ ብሏል፡-

> በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ዘንድ ለቅዱሳት መጻሕፍት ከነበረው አክብሮትና ተቀባይነት ጎን ለጎን ለቃል ትውፊትም እንደዚያው ያለ አክብሮትና ተቀባይነት ነበር። ይህ የቃል ትውፊት ከትውልድ ወደ ትውልድ በቅብብሎሽ ሲተላለፍ የነበረና ወደ ኋላ ሲሰላ ከሐዋርያት በኩል ከጌታ የተገኘ ሲሆን ከመጽሐፍ ቅዱስ ጋር የተጋጨበት አንዳችም ነገር አልነበረም። ይልቁንም ቅዱሳት መጻሕፍትን ለመተርጎም፤ በተለይም ደግሞ የክርስትና ሃይማኖትን ጠቅለል አድርጎ በመግለጽና በዚህም ክርስቲያኖችን ከግኖስቲኮችና ከሌሎች

> መናፍቃን ብረዛና ቅስጣ በመጠበቅ ረገድ ቤተ ክርስቲያንን በእጅጉ ረድቷታል። . . . ቅዱሳት መጻሕፍት እና ትውፊት በይዘታቸው አንድ የሆኑ፣ እርስ በእርሳቸው የሚመጋገቡና የሚሞላሉ ነበሩ። ይህ የቤተ ክርስቲያን አቋምም ከጥንት ጀምሮ ተሐድሶ [ፕሮቴስታንት] እስከ ተነሣበት ዘመን ድረስ የዘለቀ ነበር። . . .[22]

ካርል ቮልዝ (Carl Volz) የተባለው ደግሞ እንዲህ ብሏል፡-

> . . . ከመጽሐፍ ቅዱስ ጋር የሚስማማ ነው ተብሎ ከመታመኑ የተነሣ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነና ከመጽሐፍ ቅዱስ ጋር እኩል ሥልጣንና ተጠቃሽነት ያለው ትውፊት የቤተ ክርስቲያን አካል ነበር። በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን የኦርቶዶክሳዊነት የመጀመሪያው መለኪያ ሐዋርያዊነት (Apostolicity) ነበር፤ ይህ ሐዋርያዊነት የሚንጸባረቅባቸውና የሚገለጥባቸውም በቤተ ክርስቲያን ሐዋርያዊ ሥርዐተ አምልኮ(Apostolic Liturgy)፣ ሐዋርያዊ ቅብብሎሽ፣ ሐዋርያዊ ምስክር (ሐዲስ ኪዳን)፣ እና የሐዋርያት የእምነት አንቀጽ (the Apostles' Creed) ነበሩ።[23]

ማውሪስ ዋይልስ (Maurice Wiles) የተባለው ደግሞ እንዲህ ብሏል፡-

> በሃይማኖታዊ ጉዳዮች ላይ መጽሐፍ ቅዱስ ብቸኛው ተጠያቂና ምስክር አልነበረም። ሕያው የሆነው የቤተ ክርስቲያን ትውፊት የያዘውና ያካተተው በመጽሐፍ ቅዱስ የተጻፉትን ታሪካዊ እውነታዎች ብቻ ሳይሆን ቀጣይ የሆኑና በዘመኑም ያሉ የክርስቲያኖችን ሕይወታዊ ልምዶች ሁሉ የያዘ ነበር እንጂ።[24]

ሄንሪ ኒውማን የተባለው ቀድሞ ፕሮቴስታንት የነበረና በኋላ የቤተ ክርስቲያንን ታሪክ ሲያጠና በተወለደበትና ባደገበት በፕሮቴስታንት እምነት የተማረውና የሚያየው ነገር ሁሉ ከጥንቷ ቤተ ክርስቲያን እምነትና ሕይወት ጋር የማይስማማ መሆኑን በመረዳቱ፣ "በታሪክ ውስጥ ጠልቆ መግባት ፕሮቴስታንት መሆንን ማቆም ነው"[25] ብሏል።

[22] Robert Preus, *The View of the Bible held by the Church: Early Church through Luther*, pp. 359-360.
[23] Carl Volz, *Faith and Practice in the Early Church*, pp. 147-150.
[24] "The living tradition of the Church included not only the historical facts recorded in Scripture but also the continuing and contemporary experience of Christians." (Maurice Wiles, *The Making of Christian Doctrine: A Study in the Principles of Early Doctrinal Development*, p. 160)
[25] "*To be deep in history is to cease to be a Protestant.*", Henry Newman, Introduction, Part 5.

ትክክል ነው፤ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚል ትምህርት በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ዘንድ ያልነበረም፣ የማይታወቅም ነው። ስለዚህ ታሪክ አፍ አውጥቶ በገሃድ የሚመሰክረው እውነታ ፕሮቴስታንቲዝም ሰው ሠራሽ የሆነ ትምህርት ያመጣና ሐዋርያዊትና ኦርቶዶክሳዊት ከሆነችው ከአንዲቷ ቤተ ክርስቲያን የተለየ መሆኑን ነው። ስለዚህ በመጽሐፍ ቅዱስ ቃል የሚያምን ሰው ሁሉ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን የሰዎች የፈጠራ ትምህርት አውልቆ መጣል ይገባዋል። ሐዋርያዊ የሆነውን የቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ ተረድቶ መዳንን ገንዘብ እንዲያደርግ በመርዳት ፋንታ እያንዳንዱ ግለሰብ እንዳሻው እንዲተረጉም በማሰናበት "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ ኢየሱስ ክርስቶስ ለሰጠው የመዳን ጸጋ ታላቅ እንቅፋት የሆነና ክርስትናም በኢአማንያንና በሰነፎች ዘንድ መሳለቂያና ማፌሪያ እንዲሆን እያደረገ ያለ ጠላት የዘራው እንክርዳድ ነው።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ በተግባር ተፈትኖ መውደቁን አረጋግጧል።

ከላይ እንዳየነው 40,000 የሚሆኑ የፕሮቴስታንት አንጃዎች መኖራቸው በመጽሐፍ ቅዱስ "አንዲት ሃይማኖት" ተብሎ ከተነገረው አስተምህሮ ጋር የሚጋጭ አሳዛኝ ክስተት ነው።[26] ኤፌ. 4፡5 አንድ ዓይነት መጽሐፍ እያነበቡ 40,000 የተለያዩ ክፍልፋዮች ለምን ሆኑ? መሠረታዊ በሆኑት የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶች ላይ እንኳ አንዳቸው ከሌላቸው መስማማት ለምን አቃታቸው? ተሐድሶ የተባለው እንቅስቃሴ በተጀመረ በ80ኛ ዓመቱ የፕሮቴስታንት ድርጅቶች ከ280 በላይ ወደሚሆኑ አንጃዎች ተሰነጣጥቀው ነበር።[27] አንድ መቶ ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ እንዲህ ሲበጣጠስ ማየት እውነትን ለሚሻ ቅንነት ላለው ፕሮቴስታንታዊ ሁሉ ልብን ሊሰብር የሚገባው ነገር ነው።

በሁለት ክርስቲያኖች መካከል በአንድ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ላይ የአረዳድ ልዩነት ቢፈጠርባቸውና ቢወዛገቡ የሚዳኛቸው ማን ነው? መፍትሔያቸውስ ምንድን ነው? ከነልዩነታቸው እንዲኖሩ መተው? ወይስ ሌላ ምን ይደረግ? "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ተከታዮች ለዚህ ዓይነቱ ችግር ለመስጠት የሚሞክሩት መፍትሔ "መጽሐፍ ቅዱስን ደኅና አድርገው በጥንቃቄ ያንብቡ" የሚል ነው። ሆኖም ሁለቱም ደግመው ደጋግመው መልሰው መላልሰው የሚችሉትን ያህል ሁሉ አንብበው የደረሱበት መረዳት ግን አሁንም የተለያየ ከሆነስ ማን ይዳኛቸው?

---

[26] http://www.Christianitytoday.org

[27] Jaroslav Pelikan, *Reformation of Church and Dogma*, p. 245-246

የሁለቱን ግለሰቦች ክርክር እንዲዳኝ ሌላ ሦስተኛ ሰው ወይም ቡድን ቢመደብ ደግሞ እርሱም ከሁለቱም የተለየ የራሱን ሌላ ሦስተኛ አቋም ይዞ ሊመጣና ባሉት ልዩነቶች ላይ ሌላ ልዩነት ሊጨምርባቸው ይችላል። በእርግጥ በፕሮቴስታንት ዓለም የሆነውና እየሆነ ያለው ይኸው ነው። ሉተርን አርማለሁ ያለው ዝዊንግሊ ሌላ አቋም ይዞ ብቅ አለ። ካልቪን ደግሞ የራሱን ሌላ አስተምህሮ አመጣ። እነዚህ ሁሉ ስህተቶች ስለሆኑ ትክክለኛውን አስተምህሮ እኔ አንጥሬ አወጣለሁ ያሉት ሪፎርምድ ቸርቾች ደግሞ ሌላ ነገር ይዘው መጡ። ይኸው ሂደት አሁንም በተጠናከረ ሁኔታ ቀጥሏል። ይህ ሁኔታ የሰለቻቸው ፕሮቴስታንቶችና እነርሱን የሚያዩ ወገኖች ቢቸግራቸው "የአስተምህሮ (የሃይማኖት) ልዩነቶች ችግር የላቸውም፤ ወይም ደግሞ ልዩነቶቹ ጥቃቅን ስለሆኑ ምንም አይደሉም" ወደሚል እውነትን አንጻራዊና ግለሰባዊ ወደሚያደርግ ታላቅ ስህተት ውስጥ እየገቡ ናቸው። ሆኖም መጽሐፍ ቅዱስ ግን "እንግዲህ ከነዚህ ከሁሉ ካነሱት ትእዛዛት አንዲቱን የሚሽር ለሰውም እንዲሁ የሚያስተምር ማንም ሰው በመንግሥተ ሰማያት ከሁሉ ታናሽ ይባላል" በማለት በጽኑ ያስጠነቅቃል እንጂ የአስተምህሮ ልዩነት ችግር የለውም አይልም። ማቴ. 5፡19

የጥንቶቹ ክርስቲያኖች (በሐዋርያት ዘመንና ከዚያም ቀጥሎ በነበሩት ዘመናት የነበሩ ክርስቲያኖች) ለዚህ ችግር የሚሰጡት መፍትሔ ግልጽና የታወቀ ነው። እርሱም "ቤተ ክርስቲያን ትዳኛቸው" የሚል ነው። በቅዱስ ጳውሎስና በቢጽ ሐሳውያን መካከል ውዝግብ በተነሣ ጊዜ ቅዱሳን ሐዋርያት "ወደ ቤታችሁ ሂዱና ሁላችሁም መጽሐፍ ቅዱስን በደንብ አንብቡና እያንዳንዳችሁ በገባችሁ መረዳት ኑሩ" አላሏቸውም። ጉባኤ ሠርተው ወሰኑ እንጂ። በ4ኛው መቶ ዓመት መጀመሪያ ላይም አርዮስና መሰሎቹ ከመጽሐፍ ቅዱስ እየጠቀሱ ግን ጆሮን ጭው የሚያደርግ የክህደት ትምህርት ማስተማር በጀመሩ ጊዜ መፍትሔው "መጽሐፍ ቅዱስን በደንብ አንብቡ" የሚል አልነበረም። አርዮሳውያን መጽሐፍ ቅዱስን ከእነርሱ ወዲያ ያነበበውና የሚያውቀው ሰው ያለ አይመስላቸውም ነበርና (ይህ ብዙ ጊዜ የመናፍቃን ጠባይ ነው)። መፍትሔው የተሰጠው መጀመሪያ በእስክንድርያ በተካሄደው ጉባኤ (በ321 ዓ. ም.)፣ ቀጥሎም በኒቂያ ጉባኤ (በ325 ዓ. ም.) ላይ ነበር።

ለምሳሌም ቅዱስ አትናቴዎስ የኒቂያን ጉባኤ ውሳኔ በተመለከተ ለግብጽ ጳጳሳት በጻፈው መልእክት ላይ እንዲህ ብሏል፡-

> ስለዚህም ከእናንተ መካከል በእነርሱ [በአርዮሳውያን] የሚታለልና ልቡናው የሚማልል እንዳይኖር እማልዳችኋለሁ፤ . . . **ምንም ያህል ከመጽሐፍ ቅዱስ ቢጠቅሱና ቢጽፉ ጽሑፎቻቸውን አትታገሷቸው፤** ምንም ያህል የኦርቶዶክሳውያንን ቋንቋና ይትበሃል ቢጠቀሙም

> የሚሉትን ቁም ነገር ብላችሁ አትስሟቸው። እንዲህ የሚያደርጉት በቀና ልቡና አይደለምና፤ እንደዚህ ያሉ ቃላትንና ቋንቋዎችን እንደ በግ ለምድ በላያቸው ላይ በመደረብ በልባቸው ከአርዮስ ጋር ናቸውና፤ የኑፋቄዎች ሁሉ አባት ከሆነው ከዲያብሎስ ጋር ናቸውና። እርሱም እንዲሁ የመጽሐፍ ቅዱስን ቃላት ጌታን ለመፈተን ተጠቅሞባቸው ነበርና፤ ሆኖም ጌታችን ጸጥ እንዲልና አፉን እንዲዘጋ አደረገው እንጂ። . . . (መልእክት ኀበ ጳጳሳት ግብጻውያን፣ ቁ. 8)

ሐዋርያዊት በሆነችው ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ዘንድ ዛሬም የሚደረገው እንደዚያው የጥንቶቹ ክርስቲያኖች አባቶቻችን ሲያደርጉት እንደ ነበረው ነው። ከሶላ ስክሪፕቱራ ዋና ችግሮች አንደኛው እምነትን አንጻራዊ ወደ ማድረግ የሚመራ መሆኑ ነው። አንጻራዊነት ማለት እውነት እንደየ ግለሰቡ የተለያየ ነው፣ አንድና ለሁሉም ሰው ምን ጊዜም በየትኛውም ቦታ እውነት የሆነ ፍጹም እውነት የለም የሚል ነው። የ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" አስተምህሮ ውጤት የሆነው ይህ አስተሳሰብ፣ ዛሬ የምዕራቡን ዓለም እምነትን ተራ የሆነ ግለሰባዊ ጉዳይ አድርገው ከሚመለከቱበት ደረጃ አድርሷቸዋል። ይህ የምዕራቡ ዓለም በሃይማኖት ላይ የደረሰበት አቋም እግዚአብሔር የለሽ የሚባሉት ሶሻሊዝምና ኮሚኒዝም እንኳ ለሃይማኖት ከሰጡት ዋጋ በእጅጉ ያነሰ ነው። እነዚህ ክርስቲያኖችን እምነታችሁን ካልካዳችሁ እያሉ አሠቃዩዋቸው፣ ገደሏቸው። ይሁንና ሶሻሊዝምና ኮሚኒዝም እንደዚያ ያደረጉት ሃይማኖት ለያዘው ሰው ዋጋ ያለው ነገር መሆኑን ውስጣቸው ስለሚያምን ነበር።

ፕሮቴስታንቲዝም ሄዶ ሄዶ ያፈራው የዘመኑ የምዕራባውያን ፖለቲካዊ አስተሳሰብና አመራር ግን ሃይማኖትን እንኳንስ ሊሞቱለት የሚገባ ቁም ነገር ሊሆን ቀርቶ ተራና እዚህ ግባ የማይባል ግለሰባዊ የጓዳ ጉዳይ ብቻ አደረገው። ሃይማኖትን አንድ ሰው ስለሚለብሰው ልብስ ወይም ስለሚመገበው ምግብ ከሚያደርገው የቤት ውስጥ ተራ ምርጫ የማይለይ አደረጉት። ዛሬ እየሰማናቸው ያሉት "ሁሉም እምነት ለአማኙ ትክክል ነው"፣ "እኔ ብቻ ትክክል ነኝ ማለት ዕብሪተኝነት ነው"፣ "በማንም እምነት ላይ አትፍረድ" ወዘተ የሚሉት ምዕራባዊ አስተሳሰቦችና መፈክሮች ፕሮቴስታንቲዝም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮው በዘመናት ሂደት ወልዶ ያሳደጋቸው የልጅ ልጆቹ ናቸው።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ሥነ ምግባራዊ አንጻራዊነትንም ያስከትላል። ይህም ማለት አንድ ነገር ተገቢ ሥነ ምግባር ነው ወይም አይደለም የሚባለው፣ አንድ በሆነ በማይለወጥ አምላካዊ እውነት መለኪያነት ሳይሆን እንደየ ግለሰቡ ስሜትና አረዳድ ነው የሚል ነው። ስለዚህም ውርጃ፣ በማኅፀን ውስጥ

በሚደረግ ቅድመ ምርመራ የአካል ወይም የጤና ችግር እንዳለባቸው ተደርሶባቸዋል የሚባሉ ፅንሶችን ሳይወለዱ የመግደል ድርጊት፣ ግብረ ሰዶማዊነት፣ . . . ከባድ ኃጢአቶች መሆናቸው ቀርቶ ለእያንዳንዱ ግለሰብ የሕሊና ዳኝነት የሚተዉ "ተራ ነገሮች" ሆነው እየተቆጠሩ ነው።

ስለዚህም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ - ሶላ ስክሪፕቱራ" የሚለው የተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ መጽሐፍ ቅዱሳዊ ካለመሆኑ ባሻገር፣ ከ14ኛው መቶ ዓመት በፊት ያልነበረ፣ በተግባርም ተፈትኖ የወደቀ እና በብዙ ስህተቶች የተመላና በችግሮች የታጠረ አስተምህሮ ነው።

## 1.6 "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ("ሶላ ስክሪፕቱራ") ሲሉ ምን ማለታቸው ነው?

መጽሐፍ ቅዱስን ያከበረ የሚመስለው፣ ሆኖም ግን መጽሐፍ ቅዱሳዊ ያልሆነው ይህ አስተምህሮ ምን ማለት ነው? የሚለውን፣ እንዲሁም ደግሞ ይህ አስተምህሮ የሚያስከትለው ውጤት ምንድን ነው? የሚለውን ከዚህ ቀጥሎ እንመለከታለን።

ፕሮቴስታንቶች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ሲሉ፣ "በክርስትና አስተምህሮና ተግባራዊ ሕይወት ውስጥ አለ የሚባል ማንኛውም ትምህርት ከመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ የሚገኝ መሆን አለበት" ማለታቸው ነው።[28] "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ሲሉ በመጽሐፍ ቅዱስ መሠረታዊ የሆኑ የክርስትና እምነት አስተምህሮዎች በግልጽም ይሁን ሰወር ባለ ሁኔታ ሊገኙ ይችላሉ የሚል ቢሆን ኖሮ (Material Sufficiency of Scripture)፣ ይህ ብዙም ችግር አልነበረውም። ሆኖም ፕሮቴስታንቶች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ሲሉ ግን በዋናነት እንደዚህ ማለታቸው አይደለም። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ሲሉ "መጽሐፍ ቅዱስ አስፈላጊ የሆኑትን ሁሉንም የክርስትና አስተምህሮዎች በሙሉ የያዘ ሲሆን፣ የመጽሐፍ ቅዱስ ሐሳቡና ትርጉሙ ለማንኛውም ሰው ግልጽ በመሆኑ የመጽሐፍ ቅዱስን ሐሳብ በትክክል ለመረዳት ቤተ ክርስቲያንና ትውፊት የሚባሉ ነገሮች አያስፈልጉም" (Formal Sufficiency of Scripture) የሚለው ነው። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ዋናው ችግሩ ያለው እዚህ ላይ ነው። የክርስትና አስተምህሮዎች በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በግልጽ የተጻፉ እንዳሉ ሁሉ ከዚያ አለፍ ያሉትም ቢሆን ቢያንስ በሆነ መልኩ መልክት ተደርገውም ቢሆን ተጠቁመው ወይም ተጠቅሰው ይገኛሉ። ሆኖም ይህ ማለት ግን መጽሐፍ ቅዱስ ሁሉም ክርስቲያናዊ አስተምህሮ ለማንኛውም ሰው በእኩል በሚገባበት ሁኔታ በግልጽና በማያሻማ ሁኔታ እልቅና ድቅቅ ብሎ ተጽፎበታል ማለት ግን አይደለም።

[28] Richard A. Muller, *Dictionary of Latin and Greek Theolo*...

“መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ” ከሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ ጋር አብሮ ተከትሎ የሚመጣው ሐሳብ ደግሞ ቅዱሳት መጻሕፍትን በመተርጎም ሂደት እያንዳንዱ ግለሰብ የራሱ ፍጹም መብት አለው የሚለው ነው። የሆነ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ ምን ማለት መሆኑን በተመለከተ፣ ቅድስት ቤተ ክርስቲያን በዚያ ጉዳይ ላይ ያላት አስተምህሮ ምንም ይሁን ምን፣ እያንዳንዱ ሰው ለራሱ የራሱን ትርጓሜ የመበየንና የመወሰን መብት አለው የሚለው ነው። “መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ” በሚለው አስተምህሮ መሠረት የመጽሐፍ ቅዱስ ትርጓሜዎች፣ ምናልባት ትውፊትም ሆነ ሌላ ነገር ሊኖረው የሚችለው ሚና ግለሰቡ የራሱን ትርጓሜ እንዲወስን እንዲያግዙት ብቻ ነው። ስለዚህ እያንዳንዱ “ክርስቲያን” የግሉ የሆነ የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድና አስተምህሮ ስለሚኖረው የራሱ “ቤተ ክርስቲያን” ይሆናል ማለት ነው።

በእርግጥ ብዙው ግለሰብ እንዴ በገባባት ወይም ተወልዶ ባደገበት የፕሮቴስታንት ቡድን አረዳድና አስተምህሮ በዚያው ውስጥ ሆኖ ዝም ብሎ ይጓዛል እንጂ መጽሐፍ ቅዱስን በራሴ አንብቤ ለራሴ ልተርጉም አይልም። ሆኖም ይህን ፕሮቴስታንታዊ አስተምህሮና መብት ከምራቸው የሚተገብሩ ግለሰቦች ግን ከቡድናቸው እምነት የተለየ ከሆነ አረዳድ ላይ ከደረሱ፣ ከሚደርሱባቸው የነገረ ሃይማኖታዊ አስተምህሮ ልዩነቶች የተነሣ ቀጣዩ ተግባራቸው የሚሆነው ከዚያ ቡድን ተለይቶ መውጣትና የራሳቸውን የእምነት ቡድን (ቸርች) ማቋቋም ነው። በፕሮቴስታንቲዝም ውስጥ በብዙ ሺዎች የሚቆጠሩ የእምነት ቡድኖች የተፈጠሩት ከዚህ የ “መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ” አስተምህሮ ተፈጥሯዊ ውጤት የተነሣ ነው።

ሉተርና ካልቪንም መጽሐፍ ቅዱስን ማንም ሰው እርሱ በተረዳበት መንገድ በግሉ የመተርጎም መብት አለው የሚለውን ትምህርት እነርሱ የፈለጉትን ነገር ለማስተማር እንዲመቻቸው ለማድረግ ሲሉ ቢሰብኩትም፣ የኋላ ኋላ ግን በዚህ መርሕ ከተሄደ የሚያስከትለው ውጤት አደገኛ መሆኑ ስለገባቸው፣ እነርሱ የመሠረቱት ቡድን በመለያየቶች እንዳይናጥና እንዳይበታተን ለማድረግ ሲሉ ይህን መብት ለሌሎቹ ተከታዮቻቸው ለመከልከል ሞክረው ነበር። ግን አልቻሉም።

አንድ ነገር በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ተጽፏል ማለት፣ አተረጓጎሙንና አፈጻጸሙን ማንም ሰው በእኩልና በአንድ ዓይነት ሁኔታ ይረዳዋል ማለት ነውን? ለዚህ ማሳያ የሚሆኑ ተግባራዊ ምሳሌዎችን ከመጽሐፍ ቅዱስ እንመልከት።

**ሀ) ከሰንበት አከባበር ጉዳይ ጋር በተያያዘ በሙሴ ዘመን የተፈጠረ ችግር**

ሕጉን ከእግዚአብሔር የተቀበለው ሊቀ ነቢያት ሙሴ በሕይወት እያለ፣ እስራኤላውያን አንድ ሰው በሰንበት እንጨት ሲለቅም አገኙትና ይዘው ወደ ሙሴና ወደ አሮን

ወደ ማኅበሩም ሁሉ ዘንድ አመጡት። ያን ጊዜ ሙሴና አሮን፣ ማኅበሩም በዚያ ሰው ላይ ስላደረጉት ነገር በተመለከተ እንዲህ ይላል፡- **"ያደርጉበትም ዘንድ የሚገባው አልተገለጠምና በግዞት አስቀመጡት።"** ዐሥሩ ትእዛዛት ተጽፈው ተሰጥተዋቸው ነበር። ከዐሥሩ ትእዛዛት መካከል አንዱ "ሰንበትን አክብር" የሚለው ነው። እግዚአብሔር የሰጣቸው የሕጉ መጽሐፍ እጃቸው ላይ ነበራቸው። ታዲያ ለምን "ያደርጉበትም ዘንድ የሚገባው አልተገለጠምና በግዞት አስቀመጡት" ተባለ? ለምን በተጻፈው ሕግ መሠረት አይፈርዱበትም ነበር? እግዚአብሔርስ ሙሴን "የሕጉን መጽሐፍ ሰጥቼሃለሁ፤ ለምን በዚያው መሠረት አትፈርድም? ለምን ወደ እኔ ትመጣለህ? መጽሐፉ በቂህ አይደለምን? በነገርኩህ ውስጥ ያለውን ማንበብና መረዳት እንዴት ያቅትሃል?" ለምን አላለውም?

ከዚያም እግዚአብሔርም ሙሴን፡- "ሰውየው ፈጽሞ ይገደል፤ ከሰፈሩ ውጭ ማኅበሩ ሁሉ በድንጋይ ይውገሩት" አለው። ሙሴ ወደ ርምጃ የገባው ምን ማድረግ እንደሚገባው እግዚአብሔርን ጠይቆና መልሱን ጠብቆ ከተረዳ በኋላ ነበር። ዘኊ. 15፡32-38 ራሱ እግዚአብሔር "እኔ አፍ ለአፍ በግልጥ እናገረዋለሁ" ብሎ የተናገረለት ሙሴ እንኳ የሕጉ አተገባበርና አፈጻጸም እንዲገለጥለት ወደ እግዚአብሔር መጠየቅ ያስፈለገው ከሆነ፣ "መጽሐፍ ቅዱስ ለማንም ሰው ለመረዳት ግልጽ ነው፤ ሌላ ማብራሪያ አያሻውም" ይል ዘንድ የሚችል ከቶ እርሱ ማን ነው? ዘኊ. 12፡8 ይህ ክስተት "ሰንበትን አክብር" የሚለው ትእዛዝ በመጽሐፍ በግልጽ የተጻፈ ቢሆንም እንኳ በሕይወት የሚገጥሙ ዝርዝር ጉዳዮችን ሁሉ በሚሸፍን ሁኔታ እንዳልተጻፈ ማሳያ ነው። ስለዚህ የተጻፈውን ቃሉን እንዴት መተግበር እንዳለብን በትክክል እናውቅ ዘንድ እርዳታ ያስፈልገናል ማለት ነው። የተጻፈው ቃል በራሱ ከተጻፈው ያለፈ ነገር ሊል አይችልምና። ይህን ሊል የሚችለው ሕያውና ባለ አእምሮ የሆነው ሰው ነው። ሰው ደግሞ መረዳቱ ውስን ስለሆነ መጽሐፍ ቅዱስን እርሱ እንደ መሰለው ሳይሆን እግዚአብሔር ልንረዳ እንደሚፈልገው ለመረዳት አምላካዊ እርዳታና ምሪት ያስፈልገዋል። ይህ ደግሞ ግለሰባዊ ሆኖ ለስህተቶች በር እንዳይከፍትና ቀውስ እንዳያስከትል ቤተ ክርስቲያናዊ ሊሆን ያስፈልጋል።

ለ) "ሰው ከውኃና ከመንፈስ ካልተወለደ" **በሚለው ቃል ላይ የተፈጠሩ የአረዳድ ልዩነቶች**

ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ "ሰው ከውኃና ከመንፈስ ካልተወለደ በቀር ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ሊገባ አይችልም" ብሎ አስተምሯል። ዮሐ. 3፡5 የተጻፈልን ትምህርቱ ይኸው ነው፤ "ከውኃና ከመንፈስ ተወለዱ" የሚል። ውኃ ምንድን ነው? የውኃው ሚና ወይም ተግባር ምንድን ነው? ይህን በተመለከተ የተለያዩ አተረጓጎሞች (አረዳዶች)

ታይተዋል። መጽሐፍ ቅዱስ ግን ከላይ ከተጠቀሰው ቃል ውጭ "ውኃው ማለት እንደዚህ ነው፣ ሚናውም ይህ ነው፣ . . ." ብሎ ዘርዝሮ አብራርቶ አይናገርም። እንደዚሁ ነው የተጻፈው፣ አበቃ! ይህን የጌታን ትምህርት የጻፈልን ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊም ይህን ጉዳይ ከዚያ በኋላ ባሉት ምዕራፎች እንደገና አንሥቶ አንድም ቦታ ላይ አላብራራልንም።

ይህ ቃል ምን ማለት ስለመሆኑ ልዩ ልዩ አረዳዶች ተፈጥረው ነበር። ከእነዚህም፦

1) **አንደኛው** አረዳድ፣ "ውኃው ምልክት (symbolic) ነው፣ ዳግመኛ ከመወለድ ጋር ቀጥታ ግንኙነት የለውም የሚል ነው። ውኃው በእምነት ለሚገኘው መወለድና ከክርስቶስ ጋር ለተገኘው ኅብረት መገለጫ ምልክት፣ የቤተ ክርስቲያን አባልነቱን ለአማኞች ማሳወቂያ አንድ መንገድ ነው" የሚል ነው።

2) **ሁለተኛው** አረዳድ ደግሞ "በውኃው መጠመቅ እምነትን መመስከሪያ ነው" የሚል ነው። ይህም ማለት በውኃ መጠመቅ በክርስቶስ **ማመንን መመስከሪያ** ብቻ ነው የሚል ነው።

3) **ሦስተኛው** ደግሞ ኤፌ. 5፡26ን መሠረት በማድረግ "ውኃ የተባለው የእግዚአብሔር ቃል ነው" የሚል ነው። ስለዚህም ይኸኛው አረዳድ ውኃ በራሱ አያስፈልግም፣ ምክንያቱም ውኃ የተባለው ቃሉ ነውና ይላል። ስለዚህ ይኸኛው አረዳድ ደግሞ በውኃ መጠመቅ ጨርሶ አያስፈልግም ባይ ነው።

4) **አራተኛው** አረዳድ - በውኃ ማጥመቅ የአማኙን እምነት ለማጽናት የሚፈጸም ነው የሚል ነው። ይህም ማለት ጥምቀቱ በራሱ የሚሰጠው ጸጋ ባይኖርም እምነቱን ለማጽናት ግን ይረዳዋል የሚል ነው።

5) አምስተኛው አረዳድ ደግሞ "ውኃ አስፈላጊ ነው፣ ምክንያቱም ረቂቁን መንፈሳዊውን ልደት የምናገኘው በውኃ ስንጠመቅ ነውና" የሚል ቃሉን እንዳለ በቁሙ (በገጸ ንባቡ) የሚወስደው አረዳድ ነው።

እንግዲህ እነዚህ አረዳዶች ሁሉም "ሰው ከውኃና ከመንፈስ ካልተወለደ በቀር ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ሊገባ አይችልም" በሚለው በአንዱ የጌታችን ቃል ላይ ተመሥርተው የተፈጠሩ፣ ግን አንደኛው ከሌላኛው የተለያዩ የሆኑ አተረጓጎሞች ናቸው። ከእነዚህ ውስጥ ትክክለኛው የትኛው ነው? ትክክለኛው እርሱ ስለ መሆኑ ማረጋገጫውስ ምንድን ነው? አንድ ሰው መጽሐፍ ቅዱስን ዕድሜ ልኩን ሲያነብና ሲያጠና ቢኖር ውኃው ምልክት (symbolic) ይሁን፣ ወይም የእምነት ማጽኛ ይሁን፣ ወይም የእግዚአብሔር

ቃል ይሁን፣ ወይም የእምነት መመስከሪያ ይሁን፣ ወይም የእግዚአብሔርን ልጅነት ለማግኘት በራሱ አስፈላጊ የሆነ ነገር ይሁን አይነግረውም። ለዚህም ዘመናቸውን መጽሐፍ ቅዱስን በመማርና በማስተማር የሚያሳልፉ የፕሮቴስታንት የመጽሐፍ ቅዱስ ምሁራን ሕያው ምስክሮች ናቸው። መጽሐፍ ቅዱስን አንድ በአንድ ጥቅስ በጥቅስ እያገላበጡ ሲያጠኑ ቢኖሩም አንደኛውን አረዳድ የያዘው ሌላኛውን አረዳድ የያዘውን ከመውቀስና ከመተቸት በስተቀር ውኃ የተባለው ምን እንደሆነ አንድ ዓይነት አረዳድ ላይ ሊደርሱ አልቻሉም።

ታዲያ ምን እናድርግ? ይህን የጌታን ቃል የጻፈልንን ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊን ወደ ኋላ ሄደን "'ውኃ' ብለህ የጻፍከው ቃል ምን ማለት ነው?" ብለን ተጨማሪ ማብራሪያ እንዲሰጠን እንዳንጠይቀው እርሱ የጻፈው ይህንኑ ብቻ ስለሆነ ከእርሱ ተጨማሪ ማብራሪያ አናገኝም። ታዲያ ምን እናድርግ? ተስፋ ቆርጠን እናቁም? ለምን ብለን እንደዚያ እናደርጋለን? የቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ ደቀ መዛሙርት የነበሩትንና ከእርሱ በቃል ብቻ ሳይሆን በተግባርም የተማሩትን፣ ሐዋርያው ዮሐንስ ይህን የጌታ ቃል ምን ማለት እንደሆነ በሕይወትና በተግባር ያሳያቸውንና የተረዱትን እነ ቅዱስ ፖሊካርፐስን፣ እነ ቅዱስ አግናጥዮስን፣ እነ ቅዱስ ሄሬኔዎስን እንጠይቃቸው እንጂ! እነርሱ ሁሉም በአንድነት ተባብረው "ውኃ" የተባለው በቁሙ (literal) ውኃ ማለት እንጂ ምሳሌያዊ ወይም ምልክት (symbolic) አይደለም ይሉናል። ውኃው ለመጠመቂያነት አስፈላጊ በመሆኑና በእርሱም አማካይነት ልጅነት፣ ሥርየተ ኃጢአትና የመሳሰሉት የመዳን ጸጋዎች የሚገኙበት መሆኑን አረጋግጠው በመጻሕፍቶቻቸው ይነግሩናል። ውኃው በቁሙ ልጅነትንና ሌላውንም ጸጋ ሁሉ ለማግኘት አስፈላጊ ነው እንጂ ሊታለፍ የሚችል ተራ ነገር አይደለም ብለው በአጽንኦት ይነግሩናል።

ሆኖም ግን ይህን ጉዳይ በሥነ አመክንዮአዊ ምርምር ብቻ እደርስበታለሁ ብሎ የሚያስብ ሰው ቢኖር፣ ምናልባት ውኃ የእግዚአብሔርን ጸጋ ለማግኘት እንዴት አስፈላጊ ይሆናል? ይህ ውኃውን ምትሃታዊ (magical) ኃይል ያለው አድርጎ መውሰድ አይሆንምን? ብሎ ሊያስብ ይችል ይሆናል። ሆኖም ይህን የመሰለ አመክንዮአዊም ሆነ ሌላ ግላዊ አረዳድ ሐዋርያዊ ከሆነው የቤተ ክርስቲያን አረዳድና አተረጓጎም በተሻለ ወደ እውነቱ ሊያደርሰን አይችልም።

ቃሉን የጻፉት የቅዱሳን ሐዋርያት አረዳድና ትርጓሜ ይህ ነው። ጌታችን እኛ እናምንበት ዘንድ የፈለገውና በሐዋርያቱና ከእነርሱ እየተማሩ ለእኛ ባስተላለፉልን ተተኪዎቻቸው አማካይነት የሰጠን ይህ ነው። ይህ መሆኑን በምን እናውቃለን? ከቤተ ክርስቲያን! ከሐዋርያት ጀምሮ በቅድስት ቤተ ክርስቲያን ስለ ምስጢረ ጥምቀት የነበረው አረዳድና አፈጻጸም አንድ ነው። እንደየግለሰቡ የተለያየ ሳይሆን ውኃው

ለዳግመኛ ልደት አስፈላጊ ነው፤ በውኃ በሚፈጸም ጥምቀትም ከልጅነት ጀምሮ ብዙ ጸጋ ይገኛል የሚለው ትምህርት ከሐዋርያት አንሥቶ የነበረ እምነትና አስተምህሮ ነው። ለእኛም የደረሰው ይኸው እምነትና ትምህርት ነው። ለምሳሌም የቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ ደቀ መዝሙር የነበረው የቅዱስ ፖሊካርፐስ ደቀ መዝሙር ቅዱስ ሄሬኔዎስ እንዲህ ብሏል፦

> እኛ በኃጢአት ምክንያት አካላችን የተቆማመጠብን እንደ መሆናችን፣ የእግዚአብሔርን ስም በመጥራትና በተቀደሰው ውኃ በመጠመቅ ከክፉ በደሎቻችን ሁሉ እንነጻለን፤ አዲስ እንደ ተወለዱ ሕፃናትም በመንፈሳዊ ልደት ዳግመኛ እንወለዳለን። ራሱ ጌታችን እንዲህ ብሎ እንደ ተናገረ፦ "እውነት እውነት እልሃለሁ፣ ሰው ከውኃና ከመንፈስ ካልተወለደ በቀር ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ሊገባ አይችልም።" ዮሐ. 3፥5 (ቅሬታት፣ 34)

ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ ደቀ መዝሙሩን ቅዱስ ፖሊካርፐስን ያስተማረው እንደዚህ ነበር። ቅዱስ ሄሬኔዎስም ከመምህሩ ከቅዱስ ፖሊካርፐስ እግር ሥር ቁጭ ብሎ የተማረው ይህንኑ ነበር፤ በተግባር ያየውም እንደዚህ ነበር። ስለዚህ ቅዱስ ሄሬኔዎስም ሆነ ሌሎቹ ክርስቲያኖች ሁሉ የተረዱት ጌታችን በውኃ መጠመቅ ለዳግመኛ ልደትና መንግሥተ ሰማያት ለመግባት አስፈላጊ ነው ያለ መሆኑን ነው። በኒቂያውና በቁስጥንጥንያው የእምነት መግለጫ አንቀጽ ላይም "ኃጢአት በሚሠረይባት በአንዲት ጥምቀት እናምናለን" ተብሎ የተገለጸው ከእነርሱ በፊት ከነበሩ አባቶችና እነዚያም ከሐዋርያት፣ ሐዋርያት ደግሞ ከጌታ የተቀበሉት አተረጓጎምና አረዳድ ነው። ከዚህ ቤተ ክርስቲያናዊ አረዳድ የወጡና መጽሐፍ ቅዱስን በራሳችን መንገድ እንተረጉመዋለን የሚሉ ፕሮቴስታንቶች ግን ከዚህ ተቃራኒ የሆነ ነገር ይዘው ብቅ በማለት አንዳቸው ትክክለኛው ይኸኛው ነው፤ ሌላቸው ደግሞ እርሱ ሳይሆን እንደዚህ ነው እያሉ ሁሉም የራሳቸውን ግምት በሰዎች ላይ ለመጫን ይደክማሉ።

## ሐ) የሕፃናት ጥምቀትን በተመለከተ

መሠረታዊ በሆነው በምስጢረ ጥምቀት አስፈላጊነትና ምንነት ላይ ካላቸው የተለያየ አረዳድ በተጨማሪ ፕሮቴስታንቶች አንድ መጽሐፍ ቅዱስን እያነበቡ ሕፃናት ሊጠመቁ ይገባል ወይስ አይገባም? በሚለው ላይም እንዲሁ አቋማቸው የተለያየ ነው። መጽሐፍ ቅዱስ በግልጽ ቃል "ሕፃናት ይጠመቁ" ወይም "አይጠመቁ" አይልም። ታዲያ በዚህ ጉዳይ እርግጠኛውን ትምህርት የምናገኘው ከየት ነው? ከተባለ መልሱ ከቤተ ክርስቲያን ነው የሚል ነው። ቅዱሳን ሐዋርያት በወንጌልም ሆነ በመልእክቶቻቸው ላይ ይህን በተመለከተ በግልጽ አልጻፉልንም፤ ምክንያቱም ይህ ጉዳይ ቤተ ክርስቲያን በየዕለቱ በተግባር ስትፈጽመው የነበረና የታወቀ ጉዳይ

ስለነበረ፣ ክርክር የተነሣበት ጉዳይም ስላልነበረ ነው። በታወቀ ነገር ላይ ማብራሪያ ወይም ሐተታ መጻፍ ብዙም አስፈላጊ አይደለምና። ስለሆነም ሕፃናት ሊጠመቁ የሚገባቸው የመሆኑን ጉዳይ ቤተ ክርስቲያንና በእርሷ ውስጥ የሚኖሩ ሕያዋን ልጆቿ ያውቁታል።

ሆኖም ከቤተ ክርስቲያን ውጭ ሆነው መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ አንብበን ስለ ማንኛውም ጉዳይ ትክክለኛውን እውቀት ማወቅ እንችላለን ብለው የተነሡ ሉተርና ተከታዮቹ ግን ነገሩ እንዳሰቡት ሳይሆንላቸው ቀረና በሕፃናት ጥምቀት ጉዳይ ላይ ከሁለት ጎራ እንደ ተከፈሉ ናቸው። እነዚህም የሕፃናትን ጥምቀት የሚቀበሉ እና የማይቀበሉ ቡድኖች ናቸው።

የሕፃናትን ጥምቀት ከሚቀበሉ የፕሮቴስታንት ቡድኖች መካከል፡- ሉተራኖች፣ ፕሪስባይቴሪያኖች፣ አንግሊካኖች፣ ኮንግሪጌሽናሊስቶች፣ እና ሜቶዲስቶች ይጠቀሳሉ። ከማይቀበሉት መካከል ደግሞ አናባፕቲስቶች፣ ሞርሞኖች፣ የእግዚአብሔር ጉባኤ (Assemblies of God)፣ ዩናይትድ ቸርች ኦፍ ጎድ (United Church of God)፣ ጴንጤ ቆስጤዎች (አብዛኛዎቹ የጴንጤ ቆስጤ አንጃዎች)፣ እና ሰባተኛ ቀን አድቬንቲስት ይጠቀሳሉ።[29]

ፕሮቴስታንቶች ስለ ጥምቀት ምንነት ያላቸው አረዳድ የተለያየ ስለሆነ የሚለያዩት ሕፃናትን በማጥመቅና ባለማጥመቅ ላይ ብቻ ሳይሆን አባላቶቻቸውን ካደጉ በኋላም ቢሆን ፈጽመው የማያጠምቁና እንዲጠመቁ የማያስተምሩ፣ በእነርሱው አረዳድ ጥምቀት የሚሉትን ነገር እንኳ ጨርሶ የማያጠምቁ የፕሮቴስታንት ቡድኖች አሉ። ለምሳሌ በአሜሪካ አገር በቴክሳስ ግዛት ውስጥ ያለ አንድ የፕሮቴስታንት ቸርች ፓስተር "ክርስቶስን በእኔ ቤተ ክርስቲያን ከተቀበሉት መካከል አንድ ሦስተኛ ያህሉ አልተጠመቁም" ብሏል።[30]

ጥምቀትን ፈጽሞ አያስፈልግም ከሚሉና ከሚቃወሙ የፕሮቴስታንት ቡድኖች መካከል ደግሞ ኩዌከርስ (Quakers or Friends)፣ ክርስቲያን ሳይንስ (Christian Science)፣ እና ሳልቬሽን አርሚ (the Salvation Army) ይገኙባቸዋል። አንዳንድ ፕሮቴስታንቶችን ጥምቀት ከነጭራሹም አያስፈልግም ወደሚል ጽንፍ የገፉቸው፣ የፕሮቴስታንት ፓስተሮች በጥምቀት ላይ ያላቸው እርስ በእርሱ የሚቃረን ትምህርታቸው፣ እንዲሁም ታላቁን ነገር ተራ ነገር አድርገው መጫወቻ ሲያደርጉት በማየታቸው ስለመሆኑ የእነርሱን ሁኔታ የታዘቡ አካላት ይገልጻሉ። ይህም ፈሪሳውያን ስለ

[29] Keith E. Norman, 1992, Infant Baptism, *pp. 682–683.*

[30] Roger E. Olson, *Water Works: Why Baptism is Essential*, Christianity Today.

ትንሣኤ ሙታን የነበራቸው ትምህርት ብልሹ መሆኑ፤ ሰዱቃውያን ጨርሶ ትንሣኤ ሙታን የለም ብለው እንዲክዱ አስተዋጽኦ አድርጓል እንደሚባለው ዓይነት ነው።

**መ) ምስጢረ ቁርባንን በተመለከተ**

ጌታችን ስለ ምሥጢረ ቁርባን ሲያስተምር "ሥጋዬን የሚበላ ደሜንም የሚጠጣ የዘላለም ሕይወት አለው፤ . . . ሥጋዬ እውነተኛ መብል ደሜም እውነተኛ መጠጥ ነውና" ብሏል። ዮሐ. 6፡54-55 እንደዚሁም "ይህ ሥጋዬ ነው፤ ይህ ደሜ ነው" ብሏል። ማቴ. 26፡26-28 ይህ የጌታችን ትምህርት ምን ማለት ነው? የሚለውም፣ መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ በማንበብ እውነቱን ማወቅ እንችላለን ብለው የተነሡ የፕሮቴስታንት መሥራቾች ገና አንድ የፕሮቴስታንት ትውልድ እንኳ ሳያልፍ ራሳቸውን መሥራቾቹን እንኳ እርስ በእርሳቸው ወደ መጣላትና መወጋገዝ ያደረሳቸው ጉዳይ ሆነ።

ፕሮቴስታንቶች ሲጀምሩ ከሌሎቹ የቤተ ክርስቲያን ምስጢራት መካከል ለመቀበል የወሰኑት ጥምቀትን እና ቁርባንን ብቻ ነበር። ሆኖም እነዚህንም የምንረዳው "በቃሉ መሠረት" ነው ብለው በአዲስ መንገድ ለመረዳት ስለተነሡ አረዳዳቸው በአንጻሩ መሪ ልክ የተለያየ ሆነ። የፕሮቴስታንት መሥራቾቹ በእነዚህ ምስጢራት ላይ የ ነበራቸው አረዳድና አተረጓጎም የተለያየ በመሆኑ የተሐድሶው እንቅስቃሴ ገና ከመጀመሪያው መለያየትንና መከፋፈልን የባሕርዩ አደረገ። እንቀበላቸዋለን ባሏቸው በሁለቱ ምስጢራት ላይ የነበራቸው አለመግባባትና ልዩነት በ1520ዎቹ ላይ ጀምሮ እስከ ዛሬም እንደቀጠለ ነው።

ሁሉም የተሐድሶ እንቅስቃሴ አራማጆች "የጌታን ራት" መፈጸም አምላካዊ ትእዛዝ በመሆኑ ቢስማሙም፤ ለምን እንደሚፈጸም፣ ምን ማለት እንደሆነ፣ በመፈጸም የሚገኘው ነገርስ ምንድን ነው? በሚሉት መሠረታዊ ጉዳዮች ላይ ግን ሊግባቡ አልቻሉም። በዚህ ዋና ምስጢር ላይ የሦስቱን የተሐድሶ መሥራቾች አቋም በአጭሩ እናስታውስ።

**የማርቲን ሉተር አቋም**

የሉተር አቋም፣ "ይህ ሥጋዬ ነው" ያለው ቃል፤ እንዳለ ቃል በቃል ሊወሰድ ይገባል የሚል ነበር። ይህ ቃል ክርስቶስ በኅብስቱና በወይኑ በአማናዊ ሁኔታ ያለ መሆኑን (Real Presence)፤ እንዲሁም የኃጢአት ሥርየት የሚያስገኝ መሆኑን ያመለክታል በማለት ከነበረው ነባራዊ የቤተ ክርስቲያን ትውፊታዊ አረዳድ ብዙም ላለመራቅና በዚህ ሁኔታ ለማስረዳት ይሞክርና ይከራከር ነበር።[31]

[31] Josiah Trenham, *Rock and Sand*, p. 36.

በ1520ዎቹ መጀመሪያ ላይ ሐኪምና ሂዩማኒስት በነበረው ቆርኔሌዎስ ሁን በተባለው የደች ተወላጅ የተጻፈ ደብዳቤ ደግሞ እነዚህን የጌታን ቃላት ልንረዳቸው የሚገባው እንደ ወካዮች ወይም አመልካቾች አድርገን (symbolically) ሊሆን ይገባል አለ። ይህም ማለት "ይህ ሥጋዬ ነው" ያለውን ልንረዳው የሚገባው "ይህ ሥጋዬን ያመለክታል" እንደሚል አድርገን ነው አለ። ሉተር ይህን አዲስ አተረጓጎም በጽኑ ቢቃወመውም ዝዊንግሊና ሌሎች የተሐድሶ አራማጆች ግን በአድናቆት ተቀበሉት።[32]

### የኡልሪች ዝዊንግሊ አቋም

ኡልሪች ዝዊንግሊ የተባለው ሌላው በሉተር ዘመን የነበረው የተሐድሶ አራማጅ "ወካይ ነው" ለሚለውና ቆርኔሌዎስ ሁን አዲስ ላመጣው አተረጓጎም ዋናው ደጋፊና የሐሳቡ አራማጅ ሆነ። በዚህም ዝዊንግሊ የሉተር ተቃዋሚውና ነቃፊው፣ ዋናው ጠላቱም ሆነ። ዝዊንግሊ "የእርሱን ሥጋ የምንበላው እርሱ ስለ እኛ እንደ ሞተልን ስናምን ነው" በማለት ክርስቶስ በኅብስቱና በወይኑ የሚኖረው "በመንፈሳዊ መንገድ" (spiritual presence) ብቻ ነው አለ።[33] ማርቲን ሉተር ደግሞ "ይህ ሥጋዬ ነው" የሚለው እንዳለ በገጸ ንባቡ ሊወሰድ ይገባዋል" በማለት ይህን የዝዊንግሊን አስተምህሮ አጥብቆ ተቃወመ። ዝዊንግሊ ሲያስረዳም "ክርስቶስ በሥጋው ያረገ ስለሆነ ዳግመኛ እስከሚመጣበት ጊዜ ድረስ ሥጋው በሰማይ እንጂ በሌላ በየትም ቦታ አይኖርም፣ ስለዚህ በኅብስቱና በወይኑ ላይ የለም" አለ። ሉተር ይህን የዝውንግሊን አቋም በጽኑ ተቃወመ።

### የጆን ካልቪን አቋም

ጆን ካልቪን ደግሞ ምስጢራቱ **"ምልክቶች"** ናቸው አለ። ሆኖም **"ምልክቶች ብቻ ናቸው"** የሚለውን የዝዊንግሊን ሐሳብ ደግሞ ተቃወመ። ካልቪን አማናዊም አይደለም አለ፣ ምልክት ብቻም አይደለም አለ። ታዲያ ምንድን ነው? ሲባል ክርስቶስ "ይህ ሥጋዬ ነው" የሚሉትን ቃላት ሲጠቀም፣ የተመለከተው ነገር ስም (የሥጋው ስም) ለምልክቱ (ለኅብስቱ) ተግባራዊ ይሆንለታል" አለ።[34] ዝዊንግሊ የክርስቶስን ሥጋና ደም መብላትና መጠጣት በክርስቶስ የማመን ተለዋጭ ስም ነው ብሎ ሲከራከር፣ ካልቪን ደግሞ የክርስቶስን ሥጋና ደም መብላትና መጠጣት የማመን ተለዋጭ ስም ወይም ራሱ እምነት አይደለም፤ የእምነት ውጤት ነው እንጂ ሲል ይከራከር ነበር።

---

[32] B. J. Spruyt, 2006, *Cornelis Henrici and His Epistles on the Ecucharist: Medieval Heresy, Erasmian Humanism, and Reform in the Early Sixteenth Century, Low Countries.*

[33] Hans Joachim Hillerbrand, 2007, *The Division of Christendom: Christianity in the Sixteenth Century*. Westmnister John Knox Press.

[34] [When Christ uses the words, "This is my body," the name of the thing signified ("body") is applied to the sign (the bread).]

እንዲሁም ካልቪን የክርስቶስን ሥጋና ደም በአፋችን እንቀበለዋለን ማለት ስህተት ነው በማለት አጠንክሮ ይቃወም ነበር። ሉተርና ተከታዮቹ ግን ይህን ያምኑ ነበር። እንደ ሉተራውያን እምነት፣ ምንም እንኳ የማያምኑ ሰዎች ቢቀበሉት በራሳቸው ላይ ፍርድን የሚያመጣባቸው ቢሆንም፣ የሚያምኑም ሆኑ የማያምኑ የክርስቶስን ሥጋና ደም ሊቀበሉ እንደሚችሉ ያምኑ ነበር። ካልቪን ግን የማያምኑ ሰዎች የክርስቶስን ሥጋና ደም ፈጽሞ ሊቀበሉ አይችሉም አለ። እንደ ካልቪን እምነት የክርስቶስ ሥጋና ደም ለሁሉም ለቀረበ የሚሰጥ ቢሆንም፣ የሚቀበሉት ግን አማኞች ብቻ ናቸው።[35] ስለዚህ ካልቪን የዝዊንግሊንም፣ የሉተርንም አቋምና አተረጓጎም ተቃወመ። ካልቪን የሉተርንና የተከታዮቹን አቋም "ቅዠት" ነው ሲልም አጣጣለ። ካልቪን፣ ዝዊንግሊ እና ሉተር ሦስቱም አንዳቸው የሌላቸውን ትምህርት ኑፋቄ ነው እያሉ ተወነጃጀሉ። በእኛ አገር የተነሡ ተሐድሶ ፕሮቴስታቶችም በዚህ ምስጢር ላይ ያላቸው አቋም የብዙዎቹ የዝዊንግሊ አቋም ዓይነት ነው።

ስለዚህም ፕሮቴስታንቶች በምስጢረ ቁርባን ላይ ባላቸው የተለያየ አረዳድ የተነሣ በአውሮፓ ለብዙ ዓመታት ደም አፋሳሽ ጦርነቶች ተካሂደዋል። ሁለቱ የተሐድሶ ጠንሳሾችና ፊታውራሪዎች ሉተር እና ዝዊንግሊ በ1529 "የማርቡርግ ጉባኤ (the Marburg Colloquy)" ተብሎ በሚጠራው ስብሰባ ላይ አምርረው ተከራክረዋል። ሁለቱም ከየቡድን ተከታዮቻቸው ጋር ቢከራከሩም እርስ በእርሳቸው መስማማት ስላልቻሉ ሁለት የፕሮቴስታንት አንጃዎች በይፋ ተፈጠሩ። ሁለቱም ቡድኖች የየራሳቸውን የእምነት መግለጫ አወጡ። ዝዊንግሊ ሉተርን "እንገትህን የሚሰብርህ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ ይህ ነው" አለው። ሉተር ደግሞ "በስዊዘርላንድ እንዴት እንደሆነ አላውቅም፣ በጀርመን ግን አንገቶች እንዲሁ በቀላሉ አይሰበሩም" ብሎ መለሰለት ይባላል። ሉተር "ዝዊንግሊ ያልዳነ ነው" ይል ነበር። ዝዊንግሊ ደግሞ የሉተርን አስተምህሮ "ምትሐታዊ" እና "ጣዖታዊ መንፈስ የተቀላቀለው ነው" ይለው ነበር። ዝዊንግሊ በሉተር አስተምህሮ ላይ ያፌዝበትና ይቀልድበት ነበር። ዝዊንግሊ ሉተርን ለተሐድሶው እንቅስቃሴ ሙሉ በሙሉ ራሱን ያልሰጠና ለዘብተኛ ወግ አጥባቂ ነው እያለ ይከስሰው ነበር።

ካልቪንም መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ለሚለውና ለሌሎቹም አስተምህሮዎቹ መነሻውና ምንጩ ሉተር ቢሆንም መጽሐፍ ቅዱስን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው መርሕ በመተርጎም ረገድ ግን ሉተርን በጣም ለዘብተኛና ወግ አጥባቂ ነው እያለ ይከስሰው ነበር።[36] ሆኖም ዝዊንግሊንም የእርሱ ተከታዮች እርሱ ሉተርን በወቀሰበት ወቀሳ - ለተሐድሶው ታማኝ አይደለም፣ በበቂ ሁኔታ መጽሐፍ ቅዱሳዊ አይደለም" በሚል

[35] Calvin, *Institutes of the Christian Religion, 4.17.32-34.*

[36] Francois Wendel, *Calvin: Origins and Development of His Religious Thought*, pp. 131-135

ይወቅሱት ጀመሩ። ዝዊንግሊ እንዲህ ሲሉት ለነበሩት ተከታዮቹ በኃይልና በቁጣ ለመመለስ ቢሞክርም ውጤት ግን አላመጣም። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ነገር እንዲህ ለወላጆቹ እንኳ የማይራራ አቋኘት ነው።

ዝዊንግሊ ከጥንት ጀምሮ የመጣውን ክርስቲያናዊ ትውፊት አምርሮ ከመጥላቱ የተነሣ ዐቢይ ጾምን ሳይቀር መቃወም ጀመረ። በአንድ ወቅት ታላቁ የጌታችን ጾም በጀመረበት ቀን፣ "የክርስትናን ነጻነት ለመግለጥ ነው" በማለት በአደባባይ ሥጋ እየበላ ታየ። "የግል ጾም" የሚለውን ጽንሰ ሐሳብ ያመጣው ዝዊንግሊ ነው።[37] ከዚያ በፊት የነበረውን አምልኳዊ ሥርዓት ሙሉ በሙሉ አስወግዶ ውጥንቅጥ የሆነውን የራሱን አዲስ የአምልኮ ሥርዓት አዘጋጀ። በአጠቃላይ ከመጀመሪያዎቹ የተሐድሶ አራማጅ ትውልዶች ውስጥ እንደ ዝዊንግሊ ያለ ጽንፈኛና ነውጠኛ አልነበረም። ሉተር እንኳ "ጽንፈኛ" እስኪለው ድረስ በጣም የባሰ ጽንፈኛ ነበር። ከመምህሩ ደቀ መዝሙሩ የሚባለው ዓይነት ሰው ነበር።

ዝዊንግሊ፣ ሉተር እና ካልቪን ሁላቸውም፣ 12ቱ ሐዋርያት ከሞቱበት ጊዜ አንሥቶ እነርሱ እስከ ተነሡበት ጊዜ ድረስ እውነተኛው ወንጌል ከክርስቲያኖች ተሰውሮባቸው እንደ ነበርና ያንን የሐዋርያትን ወንጌል ከተደበቀበት ፈልፍለው ያገኙት እነርሱ መሆናቸውን በኩራት ይናገሩ ነበር።[38] ዝዊንግሊ በሚያስተምረው ትምህርት ላይ ብዙ የዙሪክ ከተማ ሰዎች ተቃውሞ ያቀርቡበት ስለነበር፣ የእርሱ ትምህርት ከሐዋርያት ወዲህ መሰል የሌለው እውነተኛው ትምህርት ስለመሆኑ ከጻፈው አንድ ማሳያ እንጥቀስ፡-

> . . . ብልህ፣ አዋቂና ደግ የሆናችሁ የተከበራችሁ ሆይ፣ የክርስቶስን ትምህርት አዲስ የሆነ ነገር ይመስል ከእናንተ እንዲለይና እንዲርቅ አታድርጉት፤ የክርስቶስ ትምህርት ከሐዋርያት ዘመን ወዲህ ልክ ዛሬ እንደ ሆነው ሆኖ ተሰብኮ በማያውቅ ሁኔታ ለእናንተ ጥርት እና ግልጽ ብሎ እየተነገራችሁና እየተሰበከላችሁ ነውና።[39]

እንግዲህ ይህን የመሰለ ትዕቢትና ዕብሪት ግን በዲያብሎስና በግብር ልጆቹ ዘንድ እንደሆነ እንጂ በአባቶቻችን ዘንድ ግን ታይቶም ተሰምቶም የሚያውቅ አይደለም። የዝዊንግሊ ውላጅነት ያላቸው አናባፕቲስቶችም "ለ1400 ዓመታት እውነቱ በሐሰት ተውጦና ተሸፍኖ ነበር" ሲሉ ከእነርሱ በፊት እውነተኛው የወንጌል ትምህርት

[37] Rock and Sand, pp. 80-81.

[38] E. J. Furcha and H. Wayne Pipkin, eds., 1984, *Prophet, pastor, protestant: The Work of Huldrych Zwingli After Five Hundred Years*,.

[39] Furcha, p. 5.

ጠፍቶ የነበረ ስለመሆኑ በ1534 ባዘጋጁት ጽሑፍ ላይ ገልጸዋል። ከእኛ በፊት ወንጌል ተሰብኮ አያውቅም ማለት የመናፍቃን አንዱ መገለጫቸው ነው።

የማርቡርግ ጉባኤ እና በፕሮቴስታንት መሥራቾች ዘንድ በምስጢረ ቁርባን ዙሪያ የተፈጠረው አለመግባባታቸው "መጽሐፍ ቅዱስ በራሱ ግልጽ ስለሆነ ማንም ሰው በማንበብ ብቻ ከትክክለኛው አስተምህሮ ላይ ለመድረስ ይችላል" የሚለው አስተምህሯቸው ደካማነቱ ምን ያህል ጥልቅ መሆኑን በተግባር የመሰከረ ክስተት ነበር። በምስጢረ ቁርባን ጉዳይ ላይ ከዝዊንግሊ ጋር በገጠመው መጠላላት ሉተር በጣም የተሰማው የነበረ ከመሆኑ የተነሣ እንዲህ አለ፡- **"ከጽንፈኞዎቹ** [ምልክት ብቻ ነው **ከሚሉት** ከእነ ዝዊንግሊና መሰሎቹ] **ጋር ባዶ ወይን ብቻ ከምጠጣ፣ ከፖፑ ጋር ደም ብጠጣ እመርጣለሁ።"**[40] ምስጢረ ቁርባን የክርስቶስ ሥጋና ደም መሆኑን የማያምኑ ዛሬ ያሉ ፕሮቴስታንቶች መሥራቻቸው ሉተር እንኳ ያምነው ከነበረው ምን ያህል የራቁ መሆናቸውንና ሉተር ዛሬ ቢነሣ እነርሱን "ጽንፈኛዎች" እንደሚላቸው ማየት፣ ሕሊና ላለው ፕሮቴስታንት ልብን የሚሰብር ነው።

ዝዊንግሊ በዚሁ ባስነሣው የሃይማኖት ጦርነት ምክንያት በ47 ዓመቱ ጦር ሜዳ በውጊያ ላይ ሳለ ተገደለ። ዝዊንግሊ ሲሞት ሉተር "በአምላክ የለሹ ላይ የተላለፈ የአምላክ ቅጣት ነው፤ የእርሱ ስህተት ጸንቶ ቢቆይ ኖሮ እኛም ቤተ ክርስቲያናችንም እንጠፋ ነበር"[41] ብሏል። አንዳንድ የዝዊንግሊ ተከታዮች ዝዊንግሊን እንደ ሰማዕትና እንደ ቅዱስ ለመቁጠር ደፋ ቀና ሲሉ ባየ ጊዜ ሉተር በመጸየፍ ሆኖ "ውይ፣ እርሱ ነው ቅዱሱና ሰማዕቱ!"[42] ሲል ተሳልቆባቸዋል።

ሉተርን እና ዝዊንግሊን፣ ካልቪንንም ሆነ ሌሎቹን ከዚያ ሁሉ ጠብና መለያየት ያደረሳቸው የሚያነቡት የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ስለ ተለያየ ሳይሆን ያንኑ አንዱን መጽሐፍ ቅዱስ የሚተረጉሙበት አተረጓጎም የተለያየ መሆኑ ነበር። ታዲያ ፕሮቴስታንቶች "መጽሐፍ ቅዱስን ማንም ሰው አንብቦ ሐሳቡን በትክክል ማወቅ ይችላል" እንደሚሉት ቢሆን ኖሮ፣ የዚህ አስተምህሮ መሥራቾቹ ራሳቸው ገና ከመነሻው ለምን እንደዚያ አምርረው ተጣሉ? የፕሮቴስታንት ተሐድሶ በውዝግብ የተወለደ፣ ለሌሎች ውዝግቦች መወለድ እናት የሆነ፣ እና ላለፉት 500 ዓመታት የማያባሩ የዕለት ተዕለት ውዝግቦችን መውለድን የቀጠለ እንቅስቃሴ ነው። የፕሮቴስታንት እንቅስቃሴ መሥራቾቹን አንድ ለማድረግ ይረዳል ተብሎ ተጠርቶ የነበው

[40] "Before I would have mere wine with the fanatics, I would rather receive sheer blood with pope." Oberman, p. 132.

[41] Philip Hughes, *A Popular History of the Reformation*, p. 139.

[42] Furcha, p. 178.

ጌታችን በማይታበል ቃሉ "ዛፍ ከፍሬዋትታወቃለችና" ብሎ ያስተማረንን ቃል ልብ ማለት ተገቢ ነው። ማቴ. 12፡33 በዚህ የጌታ ቃል መሠረት ሲታይ፣ በፕሮቴስታንቲዝም ታሪክ በገሃድ ፍጥጥ ብሎ የሚታየው ሐቅ የሚያሳየው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ዛፍ እጅግ በጣም ክፉ ፍሬ እያፈራ መሆኑን ነው። በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ የፕሮቴስታንት ቡድኖች ሁሉም ብቸኛ መመሪያችን መጽሐፍ ቅዱስ ነው፣ እኔ እውነትን እየሰብክሁ ነው፣ እኔ የምሰብከው ጌታን ነው ይላሉ፤ ሆኖም አንዳቸው የሚያስተምሩት ሌላቸው ከሚያስተምሩት ጋር አይስማማም። ፕሮቴስታንቶች ከዚህ አጣብቂኝ ለማምለጥ ሲሉ እኛ የምንለያየው መሠረታዊ ባልሆኑና በጥቃቅን ጉዳዮች ላይ ነው ብለው ለማታለል ይሞክራሉ። ሆኖም እውነታው ግን እንደዚያ አይደለም፣ ከላይ እንዳየነው መሠረታዊ በሆኑት የክርስትና ጉዳዮች ላይ፣ ለአብነት ያህልም በመዳን ላይ፣ በጥምቀት ላይ፣ በቁርባን ላይ፣ በመጽደቅ ላይ እርስ በእርሳቸው አይስማሙም። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ትክክል ቢሆን ኖሮ ፕሮቴስታንቶች ይህን ያህል ለምን እርስ በእርሳቸው ይለያዩ ነበር? መለያየታቸው ዛሬስ ለምን በየጊዜው አዳዲስ ቡድኖችን እየፈጠረ ይሄዳል?

ፕሮቴስታንቶች የመሥራቾቻቸውንና የአባቶቻቸውን ፈለግ በመከተል በምስጢረ ጥምቀት፣ በምስጢረ ቁርባንና በሌሎች ጉዳዮችም ላይ አንዳቸው ከሌላቸው እየተጣሉና በጥቅስ እየተዋጉ በየቀኑ በመለያየት አዳዲስ ዲኖሚኔሽኖችን ይፈለፍላሉ። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ሰው ሠራሽ እምነትና ትምህርት የማያስኬድ መሆኑን አሳዛኝ በሆነ ሁኔታም ቢሆን ራሳቸው ፕሮቴስታንቶች በተግባር አረጋግጠውታል። ሁላችንም መጽሐፍ ቅዱስን ገልጠን ጥቅሶቹን ማየትና ማንበብ እንችላለን፤ ችግሩ የሚመጣው ያ ያነበብነው ቃል ምን ማለት ነው? ከሚለው ላይ ነው።

እያንዳንዱ የተሐድሶ ፕሮቴስታንት ቡድንና ግለሰብ ከእርሱ በፊት የነበረውን ሌላውን "ተሳስቷል፣ የእርሱን ስህተቱን ማረም አለብኝ" ብሎ ይነሣል። ሆኖም በስህተት ላይ ስህተት እየጨመረ ከእውነተኛው የመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት እየራቀ ይሄዳል። ከሉተር ቀጥሎ ዝዊንግሊ ተነሣና ሉተርን አርማለሁ ብሎ ራሱ ሌሎች ስህተቶችን ጨመረ። ከዚያም በኋላ ወዲያውኑ ካልቪን ተነሣና ሉተር የተሳሳታቸው ነገሮች ስላሉ እኔ አርማለሁ አለ። ግን እንኳን ሊያርም የራሱን ሌላ ተደራራቢ ስህተት ጨመረበትና ስህተቱን የባሰ አገዘፈው። ከዚያም አናባፕቲስቶች እንዲሁ ከእነርሱ በፊት የነበሩትን እናርማለን ብለው ተነሡ። ከዚያ ቀጥሎ አርሚኒያኖች ተነሡ። ቀጥሎ ዌስሊያኖች ተነሡ። ሆኖም ሁሉም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" እያሉ በመጽሐፍ ቅዱስ ስም የየራሳቸውን አረዳድ በተከታዮቻቸው ላይ ጫኑባቸው እንጂ ከእነርሱ በፊት የነበሩትን ፕሮቴስታንቶች ስህተቶች ሊያርሙ አልቻሉም። ይልቁንም በችግር ላይ ችግር እየጨመሩ ሄዱ እንጂ።

“መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ” የሚለው አስተምህሮና አካሄድ ያመጣው ውጤት ቢኖር መጽሐፍ ቅዱስን የግለሰቦች መጫወቻና መዘባበቻ ማድረግ ነው። ራሳቸውን በራሳቸው መተርጉማንና የነገረ መለኮት ሊቃውንት አድርገው የሰየሙ ግለሰቦች አንድ ወይንም ጥቂት ጥቅሶችን እየመዘዙ “መጽሐፍ ቅዱስ እንዲህ ይላል” እያሉ የራሳቸውን ግላዊ አረዳድና ስሜት በመጽሐፍ ቅዱስ ሽፋን በሰዎች ላይ እየጫኑባቸው ነው። እነዚህም እጅግ በጣም አሳዛኝና ውል የለሽ ትምህርቶችን በመጽሐፍ ቅዱስ ሽፋን እያሰራጩ ይገኛሉ። ይህን ትምህርት የፈጠረው ራሱ ማርቲን ሉተር እንኳ እርሱ በቀደደው መንገድ ሌሎችም መጽሐፍ ቅዱስን በራሳቸው አረዳድ እየተረጎሙ ከእርሱ አረዳድ በተለየ መንገድ ሲተረጉሙና የተለዩ ድምዳሜዎችና ትምህርቶች ላይ ሲደርሱ በራሱ ዘመን በዐይኑ ተመልክቷል። እርሱ የፈጠረው አስተምህሮ ብዙ ዓመታትን ሳይወስድ ፍሬው ምን እንደሆነ በተመለከተ ጊዜና ነገሩ ከእጁ እየወጣ ሲሄድ ባየ ጊዜ፣ ዝዊንግሊን በመቃወም በጻፈው አንድ መልእክቱ ላይ እንዲህ ብሎ ነበር፡-

> አሁን ከሚታዩትና ካሉት የተለያዩ የመጽሐፍ ቅዱስ አተረጓጎሞች የተነሣ፣ የእምነት አንድነትን ለመጠበቅ የቤተ ክርስቲያን ጉባኤያትንና ውሳኔዎች መቀበል፣ እና መጠጊያ ይሆኑን ዘንድ ወደ እነርሱ መብረር ይኖርብናል።[43]

ሉተር “መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ” ብሎ እርሱ በቀደደው በር ገብተው ከእርሱ በባሰ ብዙ መሠረታዊ የሆኑ አስተምህሮዎችን ሲለውጡ ባየ ጊዜ ነገሩ እርሱ ከጠበቀው በላይ መፍጠኑንና ብዙ ርቀት መጓዙን ሲመለከት እነዚያን “አብዮተኞች”፣ “ጽንፈኞች” ወዘተ እያለ መውቀስ ጀምሮ ነበር። ሆኖም ሰው እንደ ውኃ ቧንቧ ሲፈልጉ የሚከፍቱትና ሳይፈልጉ ደግሞ የሚዘጉት ስላልሆነ አንዴ ከከፈተው በኋላ መልሶ መዝጋት አልቻለም።

ከሉተር አንሥቶ የነበሩት ፕሮቴስታንቶች መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ የሚለውን ካቶሊኮችን ለማጥቃት እንደ ዋና መሣሪያ ለመጠቀም ሞክረዋል። ሆኖም ይህንኑ እነርሱኑ ችግር ላይ ይጥላቸው ጀመር። ለምሳሌም ሉተር ከኤራስሙስ ጋር ባደረገው ክርክራዊ ተዋሥኦ ላይ መጽሐፍ ቅዱስ በራሱ ፍጹም ግልጽና ማንም ሰው አንብቦ ሊረዳው የሚችል ስለመሆኑ በድፍረት እንዲህ ብሎ ነበር፡-

[43] St. Francis de Sales, Th

> በገበያ ቦታ ያለው ሰው ሁሉ በግልጽ እያየው ሳለ፣ በጠባብ መንገድ ውስጥ ያሉ የተወሰኑ ሰዎች ሊያዩት አልቻሉም ተብሎ በአደባባይ ላይ ያለን ምንጭ አይታይም ብሎ ሊናገር የሚችል ሰው ማን ነው? [44]

ሆኖም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሮ ለራሳቸው በመውሰድ መተግበር በጀመሩ ጽንፈኛ ግለሰቦችና ቡድኖች ፈተና በገጠመው ጊዜ፣ ሉተር ለሁሉም ሰው ስጥቶት የነበረውን የመተርጎም መብት መልሶ መንፈግ ጀመረ። ማንኛውንም ነገር በመጽሐፍ ቅዱስ አረጋግጣለሁ ማለት አደጋ ያለው አካሄድ መሆኑን አምኖ እውቅና ሰጠ። እንዲህም አለ፡-

> የሚስማማ ሐሳብ ያላቸው ሆኑም አልሆኑም እንዲሁ ብዙ ጥቅሶችን አንድ ላይ ሰብስቦ ማጨቅ ብቻ በቂ እየሆነ መሆኑን እየተመለከትሁ ነው። የምናደርግበት መንገድ ይህ ከሆነ፣ መጽሐፍ ቅዱስን ተጠቅሜ ራስተም ቢራ ከማልምሴይ ወይን የተሻለ መሆኑን ማረጋገጥ እችላለሁ።[45] [46]

ካልቪንም እንዲሁ አድርጎ ነበር። እርሱና ሌሎቹ ፕሮቴስታንቶች "አዲስ ትምህርት እያመጣችሁ ነው" በተባሉ ጊዜ፣ ካልቪን የመለሰው መልስ "የምትታደሰውና እየታደሰች የምታድሰው ቤተ ክርስቲያን - The reformed and ever-reforming church" የሚል ነበር። ካልቪን ይህ የከፈተው በር በራሱ ዘመን እንኳ እርሱ ከሚፈልገውና ከሚለው የራቁና ተቃራኒ የሆኑ ፈጠራዎችንና ለውጦችን እየፈጠረ በማየቱ፣ ወደ ሕይወቱ መጨረሻ ገደማ ላይ የእርሱ ተከታይ የሆኑ ፓስተሮችን ሁሉንም ነገሮች ባሉበት እንዲጠብቋቸው እንጂ ምንም ነገር እንዳይለውጡ በስብከቶቹ ያሳስባቸው ነበር። ምክንያቱን ሲያስረዳም "ለውጡ እዚህ ግባ የሚባል ጥሩ ነገር አላመጣም" የሚል ነበር።[47] ይህም "እኔ እንደማደርገው ሳይሆን እንደምላችሁ አድርጉ" የሚባለው ብሒል ድንቅ ማሳያ ነው። ሆኖም እርሱ ለራሱ የሰጠውን መብት ለራሱ ያለ ገደብ ሲጠቀም ያዩት ተከታዮቹ በዚያው መንገድ በመቀጠል አንዱን ከሌላው እያስከተሉ እየለዋወጡ ከዛሬው ቅጥ ያጣ ውጥንቅጥ ደርሰዋል። ከእርሱ በኋላ ባለፉት 500 ዓመታት ውስጥ የተደረጉት ፈጠራዎችና ተሐድሶዎች ራሱ ካልቪን ካስተማረው እንኳ በጣም የራቁ ናቸው።

---

[44] E.P. Rupp, 1963, *The Bible in the Age of the Reformation*, in The Church's Use of the Bible Past and Present, ed. D.E. Nineham, p. 84.

[45] "Now I learn that it suffices to throw many passages together whether they fit or not. If this is the way to do it, I certainly shall prove with Scripture that Rastrum beer is better than Malmsey wine."

[46] E.P. Rupp, *The Bible in the Age of the Reformation*, 75-76.

[47] Herman Selderhuis, *Martin Luther: A Spiritual Biography*, p. 256

ሉተር ግን በግሉ ችግርም ሆነ በሮማ ካቶሊክ ብልሽት ምክንያት ትውፊትን ቢጠላና መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ቢልም ትውፊታዊ ነገሮችን ሙሉ በሙሉ ለማጥፋት የተነሣ ሰው አልነበረም። ሆኖም እርሱ በሩን ከፍቶ ካሳያቸው በኋላ ሌሎቹ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን ከእርሱ በበለጠ ፍጥነትና ጭካኔ እስከ መጨረሻው ጥግ ድረስ ለጠጡት። ውጤቱም በእርሱ በራሱ ዘመን በዐይኑ ያየውና እርሱን ራሱን እንኳ ያሳዘነውና ያስመረረው ሆነ። ዛሬ በዓለም ላይ ያሉት በስሙ የሚጠሩት ሉተራኖችና ፕሮቴስታንቶች እርሱ ያምነውና ያስተምረው ከነበረው እንኳ ምን ያህል እንደራቁ ቢያይ የከፈተው በር ምን ያህል የጥፋት መንገድ እንደሆነ ቀድሞ በተረዳ ነበር።

ሉተር ስለ እመቤታችን ቅድስት ድንግል ማርያም ዘለዓለማዊ ድንግልና፣ በመስቀል ምልክት ማማተብ አስፈላጊ ስለመሆኑ፣ በዓመት አንድ ጊዜ በቅጽረ ቤተ ክርስቲያን ንስሐ መግባት እንደሚገባ ያስተምር ነበር። ምስጢረ ቁርባን የክርስቶስ አማናዊ ሥጋና ደም ስለመሆኑና ጥምቀት ተአምራዊ ባሕርይ ያለው ስለመሆኑ ያስተምር ነበር። ይህን ይቃወሙ ለነበሩት ለአናባፕቲስቶችም ትዕግሥት አልነበረውም። እንደዚሁም የተጻፈ ጸሎትና መልክ ያለው ሥርዐተ አምልኮ ይጠቀም ነበር። ሕፃናትን አናጠምቅም የሚሉትን ይገሥጻቸው ነበር። እንደዚሁም ቅዱሳት ሥዕላትን ይሰባብሩና ያቃጥሉ የነበሩ ፕሮቴስታንቶችን በጽኑ ይገሥጻቸውና ይቆጣቸው ነበር። እነዚህ ክርስቲያናዊ የጥበብ ሥራዎች "ለዓይን የሚሆኑ ስብከቶች ናቸው" በማለት ስለ ተገቢነታቸው ይከራከርላቸው ነበር።[48]

ሆኖም ግን አንዴ የጀመረው የስህተት ትምህርት፣ "የምናምነው መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ ነው" እያሉ በዋና ዋና ነገሮች ላይ እንኳ የማይስማሙ የተለያዩ ቡድኖችንና ግለሰቦችን ሲያፈራ ዐይኑን በዐይኑ አይቷል። ምን ጊዜም አንድን ነገር ሲያደርጉ ከስሜትና ከእልህ ወጣ ብሎ፣ የዕለቱን ብቻ ሳይሆን ሊያስከትል የሚችለውን ነገርም ቆም ብሎ ዘለግ አድርጎ አስቦ ማድረግ ተገቢ ነው። በራሱ በሉተር ዘመን እንኳ ሁሉም "እኛ የምናምነው መጽሐፍ ቅዱስን ነው" የሚሉ ከ10 በላይ የሆኑ እርስ በርሳቸው የተለያዩ ቡድኖች ተፈጥረው በዓይኑ ተመልክቷል።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሯቸው ከእግዚአብሔር የተገኘ እውነተኛ አስተምህሮ ቢሆን ኖሮ፣ ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ ስለሚላቸው መሠረታዊ ነገሮች እንኳ እርስ በእርሳቸው የማይስማሙ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ ቡድኖችን እንዴት ሊፈጥር ቻለ? የዚህ አስተምህሯቸውና እምነታቸው ተጨባጭ ውጤቱ እንደዚህ መሆኑን በተግባር እያዩ በመሆኑ አቋማቸውን ቆም ብለው እንደገና ቢያጤኑት መልካም ነበር። ሆኖም ግን ፕሮቴስታንቶች ይህን አሳዛኝ ሁኔታ ተገንዝበው የችግሩ ሥርና

---

[48] Josiah Trenham, *Rock and Sand*, pp.51-52

መሠረት የሆነውን ነገር ከመፈለግና እርሱን ከመመልከት ይልቅ፣ የችግሩ ምክንያት ናቸው ብለው ሰበብ የሚያደርጓቸው ከዚያ ውጭ ያሉ ሌሎች ነገሮችን ነው። መፍትሔ የሚሏቸውም በተግባር የማይሠሩ መላ ምቶችን ነው።

## 1.7 የ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" አስተምህሮ ግምታዊ መላ ምቶች (Assumptions)

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሯቸው እነርሱ እንደ እውነት አድርገው በተቀበሏቸው፣ ሆኖም ግን ስህተት በሆኑ ግምቶች (assumptions) ላይ የተመሠረተ ነው። እነዚህም በዋናነት የሚከተሉት ናቸው:-

**መላ ምት ቁጥር 1:- "መጽሐፍ ቅዱስ - እምነትን፣ ሥርዐተ አምልኮን እና መሰል ሃይማኖታዊ ጉዳዮችን በተመለከተ - የመጨረሻ ቃል እንዲሆን ታስቦ የተጻፈ ነው።"**

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ ዋና መሠረታዊ እሳቤዎች አንዱ - መጽሐፍ ቅዱስ ክርስቲያናዊ ሕይወትን በተመለከተ አስፈላጊ የሆኑ ነገሮችን በሙሉ - አስተምህሮውን (Doctrine)፣ ሥርዐተ አምልኮውን (Liturgy)፣ እና ክርስቲያናዊ ሕይወትን የተመለከቱ ነገሮችን በሙሉ ይዟል፣ ስለዚህ ሌላ ነገር አያስፈልግም የሚል ነው።

ቅድስት ቤተ ክርስቲያን የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍትን ስምና ዝርዝር ሰፍራና ቆጥራ በቀኖና የወሰነችበት ዋናው ምክንያት መናፍቃን በሐዋርያት ስም እየጻፉ ያሠራጯቸው ከነበሩት እውነትና ሐሰትን አቀላቅለው ከያዙት የግኖስቲኮች ድርሰቶች ለመጠበቅ ነበር። ሆኖም የቀኖናውያት መጻሕፍትን ዝርዝር ለይታ ያስቀመጠችው ግን የክርስትና አስተምህሮን፣ ሥርዐተ አምልኮንና ክርስቲያናዊ ሕይወትን በተመለከተ አስፈላጊ የሆነው ሁሉም ነገር በሙሉ ተጠቃልሎ በውስጡ ተጽፏል በሚል አይደለም። ብዙዎቹ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት የተጻፉት የሆነ ዋና ጉዳይን ማዕከል አድርገው ያን ጉዳይ በሚያስረዳ እና ተነሥተው ለነበሩ ጥያቄዎች መልስ በሚሰጥ ሁኔታ ነበር። የቅዱስ ጳውሎስ መልእክታትን ስንመለከት ሁሉም ማለት በሚቻል መልኩ የተጻፉት በዘመኑ ለተነሡ የአስተምህሮ፣ የሥርዐተ አምልኮና ክርስቲያናዊ ሕይወት ጉዳዮች መልስና መፍትሔ ለመስጠት ነበር። የሮሜ መልእክት፣ ሁለቱ የቆሮንቶስ መልእክቶች፣ . . . የተጻፉበት ምክንያት (ምክንያተ ጽሕፈት) ነበራቸው።[49]

[49] ቅዱስ ዮሐንስ አፈ ወርቅ፣ ትርጓሜ ግብረ ሐዋርያት፣ ክፍል ትምህርት 1፣ ) ገጽ 202 ተመልከት

መልእክቶቹ በተጻፉበት ወቅት ላይ ጥያቄ ባልተነሣባቸው ጉዳዮች ላይ፣ ጥያቄ የሆነው የተነሡትን ጉዳዮች ሲመልሱና ሲያብራሩ ወይም እግዚአብሔር ባወቀ በዚያው በኩል እግረ መንገድ የተዳሰሱ ካልሆኑ በቀር፣ ስለ እነዚያ ነገሮች በቀጥታ በዝርዝርና በጥልቀት ብዙም አልተጻፈም። ስለዚህ ቅዱሳን ሐዋርያት በሁሉም ዘንድ የታወቁና የተረዱ ናቸው፣ ችግሮችም አይደሉም ብለው ባሰቧቸው ጉዳዮች ላይ በዝርዝርና በጥልቀት ትምህርትና ማብራሪያ አልጻፉባቸውም። በግልጽና ሰፋ ባለ ሁኔታ የተጻፈባቸው ነገረ ሃይማኖታዊ ጉዳዮች በዋናነት ክርክር የተነሣባቸው ወይም አለመግባባት የተፈጠረባቸው ወይም ደግሞ የተሳሳተ አረዳድ የታየባቸው ጉዳዮች ነበሩ። ለምሳሌም ስለ መጽሐፍ ቅዱስ ከስህተት ነጻ መሆን በተመለከተ ብዙም በግልጽ የተባለ ነገር አናገኝም፣ ምክንያቱም መጻሕፍቱ ሲጻፉ ይህ የታወቀና የታመነ ነገር በመሆኑ ጥያቄ አልነበረምና ነው። ሆኖም በምዕራቡ ዓለም ይህን ጉዳይ ዋና ጉዳይ አድርገው የተነሡ ስኬፕቲሲስቶች በመጡበት በእኛ ዘመን ቢጻፉ ኖሮ ምናልባት በዚህ ጉዳይ ላይ ብዙ ነገር ተጽፎ ልናገኝ እንችል ይሆን ነበር። ሆኖም ይህን ጉዳይ በተመለከተ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በግልጽና በዝርዝር ስላልተጻፈ የጥንት ክርስቲያኖች አያውቁትም ወይም አያምኑበትም ነበር ማለት አይደለም፣ ጉዳዩ ሊጻፍለት እስከማያስፈልገው ድረስ የታወቀና የታመነ ስለነበር ነው እንጂ።

ከዚህ በላይ ደግሞ ሥርዐተ አምልኳዊ ነገሮች የተዳሰሱት ተዛማጅ ችግሮች አብረው ያሉባቸው ሆነው ሲገኙ ብቻ ነበር (ለምሳሌ 1 ቆሮ. 11-14)። በሐዲስ ኪዳን ከተጻፉት መጻሕፍት መካከል አንዳቸውም ቢሆን በቤተ ክርስቲያን የሚፈጸመው ሥርዐተ አምልኮ **ከመጀመሪያው እስከ መጨረሻው ድረስ** እንዴት እንደሚፈጸም ለመግለጽ ታስበው አልተጻፉም። ለምን? ከተባለ እርሱ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ በሕይወት እየተኖረና እየተከወነ ስለነበረ ነው። በሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት በየመካከሉ ከሌላ ጉዳይ ጋር ተጫፍረው በፍንጭ ሰጭነት ብልጭ እያሉ ከተነገሩ ጥቂት ማሳያዎች በስተቀር ስለ ጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ሥርዐተ አምልኮ ከመነሻው እስከ መድረሻው ምን እንደነበር በዝርዝር ተጽፎ አናገኝም። ይህ ለምን ሆነ? ብንል የአምልኮው ሂደት ሥርዓት ስላልነበረው ሳይሆን ሐዋርያውያን የሆኑ አብያተ ክርስቲያን ሁሉ ከቅዱሳን ሐዋርያት በወረሱት መሠረት ሥርዓተ አምልኳቸውን ይፈጽሙ ስለነበር መሆኑን የሥርዐተ አምልኮ ጥናት ምሁራን በሚገባ አረጋግጠዋል።[50]

እንደዚህ ሆኖም ግን ሥርዐተ አምልኮን በተመለከተ በሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ ተገልጸው የምናገኛቸው ነገሮች የሚያሳዩት በፕሮቴስታንቱ ዓለም እንደሚታየው ፓስተሩ በፈለገው ሁኔታ በየሳምንቱ የሚቀያየርና በብዙዎቹ ዘንድ የሚታየው

[50] Alexander Schmemann, *Introduction to Liturgical Theology, pp.* 51 ff.

ከእብደት ያልተናነሰ ነገር የሚፈጸምበት ሳይሆን የሐዲስ ኪዳን ክርስቲያኖች የመልኩ የነበረው ከሐዋርያትና ከእነርሱ ከወረሱ አባቶች ባገኙት መሠረት በአግባብና በሥርዓት የነበረ መሆኑን ነው።

ከዚህም ጋር ልብ ልንለው የሚገባ ነገር ቢኖር የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት አንዳቸውም ቢሆን ወጥ የሆነ ክርስቲያናዊ አስተምህሮን (ዶክትሪንን) ሰፍሮና ቆጥሮ ሁሉንም አንድ በአንድ ዘርዝሮ የማስረዳት ዓላማን ይዘው የተጻፉ አለመሆናቸውን ነው። የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት የተጻፉት ለንዑስ ክርስቲያኖች እንደሚሰጥ ዓይነት ማስተማሪያ ወይም ደግሞ ወጥ በሆነ ነገረ አምላካዊ የትምህርት መልክ (systematic theology) አይደለም። እንደዚያ ቢሆንማ ኖሮ በኒቂያና በቁስጥንጥንያ ጉባኤያት ላይ የቤተ ክርስቲያንን መሠረታዊ አስተምህሮና እምነት የሚገልጽ አንቀጽ ለማርቀቅ ያን ያህል ድካም ባላስፈለገ ነበር። እግዚአብሔር መጽሐፍ ቅዱስን ያስጻፈልን የማይወሰነውን ነገረ አምላካዊ ጉዳይ አንድ ሁለት በማለት ወስኖና ገድቦ በሚነግረን መንገድ አይደለም። ክርስቲያኖች የሚፈልጉት "መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ" ቢሆን ኖሮ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ወጥ የሆነ ነገረ ሃይማኖታዊ አስተምህሮን ነጥብ በነጥብ የሚዘረዝር የእምነት መግለጫ ዓይነት አንቀጽ ለምን የለም? መጽሐፍ ቅዱስ በእንደዚያ ዓይነት መልኩ ተጽፎ ቢሆን ኖሮና እያንዳንዱን አስተምህሯዊ ጥያቄ በሚመልስ ዓይነት አጻጻፍ ተጽፎ ቢሆን ኖሮ፣ ስንት አወዛጋቢ ነገረ ሃይማኖታዊ ጥያቄዎች በቀላሉ በተመለሱ ነበር። ሆኖም እግዚአብሔር ያስጻፈልን በዚህ መንገድ አይደለም። ይህን መረዳት መሠረታዊ ነገር ነው።

እዚህ ላይ ለማለት የተፈለገውን በአግባቡ እንረዳ። እዚህ ላይ እያልናቸው ካሉት ነገሮች መካከል አንዳቸውም ቢሆን የመጽሐፍ ቅዱስን አስፈላጊነትና ጥቅም የሚያቃልሉ አይደሉም። በጭራሽ! መጽሐፉን በአግባቡና በትክክለኛው ሁኔታ እንረዳውና እንጠቀምበት ዘንድ ለመርዳት አስፈላጊ የሆኑ ነገሮች ናቸው እንጂ። መጽሐፍ ቅዱስ "የእግዚአብሔር እስትንፋስ"፣ "በመንፈስ ቅዱስ ምሪት የተጻፈ"፣ "ስህተት የሌለበት"፣ በአጠቃላይ "መጻሕፍት አምላካውያት" ተብለው ልዩ ቦታና ክብር የሚሰጣቸው ቅዱሳት መጻሕፍት መድበል ነው።

ይህ እንዳለ ሆኖ መጽሐፍ ቅዱስ በውስጡ ባሉት መጻሕፍት ውስጥ ቤተ ክርስቲያን አስፈላጊዋ በሆኑት ጉዳዮች ሁሉ ላይ ማንኛውም ሰው በራሱ አንብቦ ሊደርስበት በሚችል ሁኔታ ዝርዝር ትምህርትን የያዘ ግን አይደለም። ሆኖም ቤተ ክርስቲያን ቅዱሳት መጻሕፍትን መርጣ፣ በቀኖና ወስና ስትሰጠን አምነን እንደተቀበልናት ሁሉ፣ ሥርዐተ አምልኮን በተመለከተ በተግባራዊ ሕይወት የሰጠችንንም አምነን መቀበል የግድ ይላል። ከእርሷ የተገኙትን ቅዱሳት መጻሕፍት አምኖ ተቀብሎ

ሥርዐተ አምልኮዋን አልቀበልም ማለት አግባብነት አይኖረውምና። ሥርዓተ አምልኮዋን ካላመንን ይህች ቤተ ክርስቲያን የመረጠቻቸውን መጻሕፍት እንዴት ማመን ይቻላል?

ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስ ነገረ ክርስትናንና ሥርዐተ አምልኮን እንዲሁም መሰል ሃይማኖታዊ ጉዳዮችን በተመለከተ ስለ ሁሉም ነገር አስፈላጊ የሆነውን ዝርዝር ትምህርት የያዘ ሆኖ የተጻፈ በመሆኑ ብቻውን በቂ ነው የሚለው መላ ምታቸው ከእውነት የራቀ ግምት ነው።

**መላ ምት ቁጥር 2፡- "የመጀመሪያ ቤተ ክርስቲያን መሠረቷ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ነበር፣ ትውፊት ግን ወደ ኋላ ላይ ሰዎች የፈጠሩት ስሁተት ነው።"**

በአብዛኞዎቹ ፕሮቴስታንቶች ዘንድ "ትውፊት" የሚለው ቃል በበጎ አይታይም። አንድን ነገር "ትውፊት" ብሎ መሰየም ያንን ነገር "ሥጋዊ"፣ "ጐታች"፣ "በመንፈስ የሞተ"፣ "ተረት ተረት"፣ "አፍራሽ"፣ ወይም "ሕግ ተኮር" ነው እንደ ማለት አድርገው ይቆጥሩታል። ፕሮቴስታንቶች፣ መጽሐፍ ቅዱስ ትውፊትን የሚነቅፍና የሚያወግዝ መስሎም ይሰማቸዋል። ከእኛው አገር ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች አንዱ "ድኅነት ወይስ ትውፊት?" ብሎ የጻፈውም የዚሁ መንፈስ ውጤት ነው።

በተለይም ደግሞ ኢቫንጄሊካል (ወንጌላውያን) እና ካሪዝማቲክ (የጴንጤ ቆስጤ ዝርያዎች)፣ ለእነርሱ የመጀመሪያዎቹ ክርስቲያኖች ማለት ልክ በ21ኛው መቶ ክፍለ ዘመን ያሉት እነርሱ እንደሆኑት ዓይነት የነበሩ ይመስላቸዋል። የመጀመሪያው መቶ ዓመት ክርስቲያኖች ሥርዐተ አምልኮ የነበራቸው መሆኑን ወይም ትውፊት የነበራቸው መሆኑን ፕሮቴስታንቶች መቀበል አይፈልጉም። እንደ እነርሱ እምነት ከሆነ ሥርዐተ አምልኳዊና መሰል ትውፊቶች ቤተ ክርስቲያን "እየተበላሸች ስትሄድ" ወደ ኋላ ላይ ሰርገው ውስጧ ገቡባት እንጂ ከመጀመሪያው ጀምሮ ግን አልነበሩም ባዮች ናቸው።

ሆኖም እውነታው ግን እነርሱ እንደሚያስቡት ሳይሆን የመጀመሪያዋ ቤተ ክርስቲያን ሥርዐተ አምልኮዋንና ሕይወቷን የሚመራ ሐዋርያዊ ትውፊት ነበራት።[51] ከሐዋርያት ቀጥሎ የተነሡት ሐዋርያውያን አበውና ከዚያም በመቀጠል የተነሡ አባቶች ያስተማሯቸውን ትምህርቶች የሚያጠና ማንም ሰው ቢሆን ይህን እውነታ በቀላሉ መረዳት የሚችለው ነገር ነው። በዚህ ጉዳይ ላይ የሐዲስ ኪዳን ምስክርነትም ግልጽ ነው። ክርስቲያኖች ከጌታ በሐዋርያት የተቀበሏቸው የተጻፉና የቃል ትውፊቶች

[51] Schmemann, *Introduction to Liturgical Theology*, pp. 51 ff.

የነበሯቸው መሆኑ በግልጽ የተጻፈ ነው። የሐሰት "ወንጌሎች" እና "መልእክቶች" ይሰራጩ ስለነበር እውነተኞቹን ወንጌሎችና መልእክቶች ለመለየት ያስቻላቸው የጌታችን ትምህርት በቃል ትውፊት ስለነበራቸው ነው።

እነዚያ ክርስቲያኖች የተሟላ መጽሐፍ ቅዱስ ስላልነበራቸው እንዴት አምልኮ እንደሚፈጽሙ ያውቁ የነበረው ከተጻፈ መጽሐፍ ብቻ ሳይሆን ስለ ክርስቶስ ትምህርት ከቅዱሳን ሐዋርያት የተቀበሉት ተግባራዊ የሕይወትና የቃል ትውፊት ስለነበራቸው ነው። በተለይ ቀደም ያሉት ክርስቲያኖች በአብዛኛው ስለ ክርስትና የሚያውቁበት ምንጫቸው የቃል ትውፊት ነበር። ይህ በቃል ትውፊት ላይ የነበረው መመሥረት በራሳቸው በሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ላይም በግልጽ ጎልቶ የሚታይ ነው። ቅዱስ ጳውሎስ "በቃላችንም ቢሆን ወይም በመልእክታችን የተማራችሁትን ወግ ያዙ" እንዳለ። 2 ተሰ. 2፥15 ስለዚህ ፕሮቴስታንት ወገኖቻችን እንደሚገምቱትና እንደሚመስላቸው ትውፊት በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ያልነበረና ወደ ኋላ በሆነ ዘመን ላይ ብቅ ያለ ነገር አይደለም። ከራሱ ከጌታችንና ከሐዋርያት ጀምሮ የነበረ የቤተ ክርስቲያን የትምህርቷና የሕይወቷ አካል ነው እንጂ።

የመጀመሪያዋን ቤተ ክርስቲያንና የቀደምት አባቶችን ጽሑፎች ያጠኑ ብዙ ፕሮቴስታንቶች ያገኙት እውነታ ባደጉባቸው የፕሮቴስታንት ቸርቾች ሲነገራቸው ከነበረው ጋር ፊት ለፊት የሚጋጭ ሆኖ እያገኙት ስለሆነ የመጀመሪያዋን ቤተ ክርስቲያን ትምህርትና ሕይወት ወደ ያዘችው ቤተ ክርስቲያን - ወደ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን በመምጣት ላይ ያሉ ብዙዎች ናቸው። ብዙ የፕሮቴስታንት የነገረ ሃይማኖት ምሁራን የጥንቷን ቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ፣ ይትበሃልና ሥርዐተ አምልኮ ሲያጠኑ የምዕራቡ ዓለም ምን ያህል ከዚያ መሠረት እንደ ራቀና ከሀብቷ እንደ ተራቆተ እየተገነዘቡ ነው።

ለምሳሌም አባቱ ታዋቂ የፕሮቴስታንት ሰባኪና ፓስተር የነበረው፣ እርሱ ደግሞ ደራሲና የፊልም ዳይሬክተር የሆነው ፍራንክ ሻፈር (Frank Schaffer) የተባለው አሜሪካዊ፣ ተወልዶ ባደገበት በፕሮቴስታንቲዝም አስተምህሮና ሕይወት ውስጥ የጥንቷን ቤተ ክርስቲያን ትምህርትና ሥርዐተ አምልኮ ፈልጎ ፈልጎ ሊያገኝ ባለመቻሉ፣ ያችን የጥንቷን ቤተ ክርስቲያን ትምህርትና ሕይወት የያዘችውን ቤተ ክርስቲያን ለማግኘት ከቸርች ቸርች እየተንከራተተ ብዙ ዓመታትን የወሰደ ፍለጋ አድርጓል። በመጨረሻም በመጽሐፍ ቅዱስ የተገለጹትንና በጥንት የቤተ ክርስቲያን አባቶች ትምህርቶች የሚገኙትን ትምህርቶችና ሥርዐተ አምልኮዎች አጠቃላይ ሕይወትና መንፈስ ያገኘው በኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ በመሆኑ ወደ ጥንቷ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ተጠምቆ ገብቷል። ይህን ያደረገውን ፍለጋና በሂደቱ

የገጠሙትን ነገሮች በተለያዩ ንግግሮቹና መግለጫዎቹ ላይ በኢንተርኔት ማግኘትና መስማት ይቻላል። "Dancing Alone"፣ "A Letter to Father Aristotle" የተሰኙና ሌሎች ጠቃሚ መጻሕፍትንም ጽፏል።[52]

እንደዚሁም ጆሲያስ ትሬንሃም (Josiah Trenham) የተባለው በፕሮቴስታንት ቸርቾች ተወልዶ ያደገና እስከ ዶክትሬት የተማረ ሲሆን፣ እርሱም እንደዚሁ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን የነበረውን አስተምህሮና ሥርዐተ አምልኮበፕሮቴስታንት ቸርቾች ፈልጎ ፈልጎ ሊያገኘው ስላልቻለ፣ ከብዙ ድካም በኋላ ወደ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ተቀላቅሏል። አሁን ሊቀ ካህናት ሆኖ በክህነት እያገለገለ ይገኛል። የፕሮቴስታንት ቸርቾችን ከመነሻቸው ጀምሮ ምንነታቸውን ጥሩ አድርጎ የሚያሳይ "Rock and Sand" – An Orthodox Appraisal of the Protestant Reformers and Their Teachings) የሚል ርእስ ያለው መጽሐፍም ጽፏል።

በአሜሪካ አገር ሉተራኒዝምና ሌሎቹም የፕሮቴስታንት ቡድኖች በፍጥነት ወደ መጥፋት እየሄዱ ናቸው። በጣም ብዙ ፕሮቴስታንቶች ወደ ቸርቾቻቸው መሄድንና እምነታቸውን መኖርን እርግፍ አድርገው እየተዉ ናቸው። የሚሄዱትም ከአምልኮ ይልቅ ለመዝናናት ዓይነት እየሆነ ሄዷል። ከእነዚያ ውስጥ ተስፋ ሳይቆርጡ እውነትን የፈለጉት ደግሞ ሐዋርያዊቷን ቤተ ክርስቲያን እያገኟት ናቸው። ባለፉት ሠላሳ ዓመታት ውስጥ ብዙ ሉተራን ምእመናንና ካህናትም ወደ ኦርቶዶክሳዊነት ገብተዋል።[53]

ስለዚህ ይህ "የመጀመሪያዋ ቤተ ክርስቲያን መሠረቷ መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ነበር፣ ትውፊት ግን ወደ ኋላ ላይ ሰዎች የፈጠሩት ስህተት ነው" የሚለው የፕቴስታንቶች ግምት ከእውነተኛው የቤተ ክርስቲያን ሕይወትና ታሪክ ጋር የሚጣላ ስህተት ነው። ፕሮቴስታንቶች ትውፊትን አምርረው የሚቃወሙበት ምክንያት መሥራቾቻቸው እነ ሉተር ያገኙትና የሚያውቁት ትውፊት በሮማ ካቶሊክ ቤተ ክርስቲያን የነበረውን ትውፊት ስለነበር ነው። በሮማ ካቶሊክ አስተምህሮ መሠረት ትውፊት የሚወከለውና የሚገለጸው በፖፑ ሲሆን "ትውፊት ያድጋል፣ ይጎለምሳል" በሚለው አስተምህሯቸው መሠረት ቀድሞ ያልነበሩ አዳዲስ ትምህርቶችንም በየጊዜው ይፈጥራሉ (ለምሳሌ የፖፑ የማይሳሳት መሆን ትምህርት)። በኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ዘንድ ግን የቤተ ክርስቲያን ራስ ኢየሱስ ክርስቶስ እንጂ ፓትርያርክ አይደለም።

---

52 "Dancing Alone" በተሰኘው መጽሐፉ ላይ ተወልዶ ባደገበት በፕሮቴስታንቲዝም ውስጥ በፓስተሮቹ ስሜት ላይ ብቻ የተንጠለጠለው መነሻውና መድረሻው የማይታወቀው ስሜትና ጩኸት የነገሠበት "አምልኮ" ምን ያህል አሳዛኝ ስለመሆኑ፣ በአጠቃላይ ሐዋርያዊቷን ቤተ ክርስቲያን ፍለጋ ለምን እንደ ተነሣና ያለፈባቸው የፍለጋ ጉዞዎች ምን ይመስሉ እንደ ነበር ያሳያል።

53 Josiah Trenham, *Rock and Sand*, p.68

ትውፊት የሚገለጸውና የሚወከለውም ጉባኤያዊት በሆነችው በቤተ ክርስቲያን እንጂ በግለሰብ አይደለም። ቤተ ክርስቲያን የስህተት ትምህርት ሲገጥማት እውነቱን ከስህተቱ ለመለየት በሚረዳ መንገድ አስተምህሮዋን ትገልጣለች እንጂ እውነቱ አይቀየርም፣ እውነቱ ምን ጊዜም ያው ነው። ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ለሚለው አስተምህሯቸው መሠረት ያደረጉት ይኸኛው ግምታቸውም ስህተት በመሆኑ እናዝናለን።

**መላ ምት ቁጥር 3፡- "ማንም ሰው የማንም እገዛ ሳያስፈልገው መጽሐፍ ቅዱስን አንብቦ ለራሱ መረዳት ይችላል።"**

የተሐድሶ መሥራቾች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ሲሉ መጽሐፍ ቅዱስ ትርጕሙ በጣም ግልጽ ከመሆኑ የተነሣ ማንም ሰው አንብቦ ሊረዳው ይችላል የሚል ሲሆን፣ ይህን አቋማቸውንም ሉተር በሞተ በ30ኛው ዓመት ገደማ፣ የቱቢንጌን የፕሮቴስታንት ምሁራን ከቁስጥንጥንያው ፓትርያርክ ከኤርምያስ 2ኛ ጋር መልእክት ሲለዋወጡ ገልጸውታል፡-

> . . . ቅዱሳት መጻሕፍት . . . መንፈስ ቅዱስ የመራቸው አባቶች ከጻፏቸው ትርጓሜዎች ውጭ [ያለ እነዚህ ርዳታ] በግልጽ ለመረዳት የማይቻሉ እስኪሆኑ ድረስ በብዙ ስውር ነገሮች ተሸፍነዋል የሚል ይኖር ይሆናል። . . . ሆኖም በቅዱሳት መጻሕፍት ውስጥ በአንድ ቦታ ላይ ለመረዳት በሚቻል ሁኔታ በግልጽ ያልተነገረው ነገር፣ **ማንኛውም ተራ ሰው እንኳ በቀላሉ ሊረዳው በሚችለው ሁኔታ በሌላ ቦታ ላይ በግልጽ ተጽፏል።**[54]

ሆኖም ግን፣ እነርሱ እንደሚሉት ሁሉም ሰው መጽሐፍ ቅዱስን አንብቦ ያለ ማንም ርዳታ በትክክል መረዳት የሚችል ከሆነ፣ መሠረታዊ በሆነው በመዳን ጉዳይ እንኳ ለምን ይህን ያህል መለያየት ተፈጠረ? ሆኖም እውነታው ቢመርራቸውም መካድ ስለማይችሉ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሯቸው የሚያስገኘው ውጤት ሁል ጊዜም መለያየትንና ክርክርን ስለሆነባቸው ብዙ ፕሮቴስታንቶች "አንዲት ሃይማኖት" የሚለውንና "አንዲት ቤተ ክርስቲያን" የሚለውን የመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት እውነተኛ እንዳልሆነ ነገር እየወሰዱት ከመጡ ውለው አድረዋል። ጌታችን የመሠረታት ቤተ ክርስቲያን አንዲት ብቻ ስለመሆኗ እና ሃይማኖትም አንዲት ናት ተብሎ በግልጽ ከተነገረው ትምህርት ጋር ፊት ለፊት ሲጋፈጡ "እንደዚህ የሚሉ ነገሮች ለክርስቲያናዊ ፍቅር ጥሩ አይደሉም"፣ "ዋናው ፍቅር ነው"፣ "በጌታ አንድ ነን" በሚሉና ይህን በመሰሉ ነገሮች ራሳቸውን ለማታለል ይሞክራሉ። እውነተኛው

[54] George Mastrantonis, trans., *Augsburg and Constantinople: the Correspondence between the Tübingen Theologians and Patriarch Jeremiah II of Constantinople on the Augsburg Confession*, 115.

እምላካዊ ፍቅር ግን እውነትን በመሠዋት ሊገኝ አይችልም። ሐዋርያው እንዳለ "እውነትን በፍቅር እንይዛለን" እንጂ ከእውነት ውጭ ፍቅር ሊኖረን አይችልም።

ሐዋርያዊት በሆነችው አንዲት ቤተ ክርስቲያን እምነትና ትምህርት ላይ የቆመ እውነተኛ አንድነት ስለሌላቸው የውሸት አንድነት ለመፍጠር ይሞክራሉ። ለዚህም "የወንጌላውያን ኅብረት"፣ "የጌታ አማኞች አንድነት"፣ "የሥላሴ አማኞች ኅብረት"፣ የመሳሰሉ ድርጅቶችን በመፍጠር ክርስቲያናዊ አንድነት እንዳገኙ በማሰብ ራሳቸውን ይሸነግላሉ። እያንዳንዱን የፕሮቴስታንት ቡድን "በአንድ ዛፍ ላይ ያለን ቅርንጫፎች ነን" በማለት ከሐዋርያዊቷ ቤተ ክርስቲያን አስተምህሮና ሕይወት በመለየታቸው ያጡትን አንድነታቸውን እንደ የዓለም አብያተ ክርስቲናት ኅብረት በመሳሰሉ ሰው ሠራሽ ድርጅቶች በኩል የሚያገኙት ይመስላቸዋል።

እነዚህ ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን ዋናውን እምነታቸውን የመሠረቱባቸው መሠረታዊ እሳቤዎች ወይም ግምቶች እንዲህ የተሳሳቱ ናቸው። ስለዚህም ይህ አስተምህሮ በምናብ እንጂ በእውነታው ዓለም ውስጥ ህልውና የሌለው ትምህርት ነው።

## 1.8 መፍትሔ ብለው የሚያቀርቧቸው የአነባበብ መርሖች

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ትምህርት ገና ከመነሻው ጀምሮ መለያየትንና መከፋፈልን በመፍጠሩና ችግሮቹም በፍጥነት እየሰፉ በመሄዳቸው ስህተትነቱን ከመናገርና በግልጥ ከማሳየት አልቦዘኑም ነበር። ሆኖም ፕሮቴስታንቶች ግን የአስተምህሯቸውን ስህተትነት ተረድተው እውነቱን ከመቀበል ይልቅ ችግሩ መጽሐፍ ቅዱስን የሚያነብቡት ሰዎች ችግር ነው በማለት እውነታውን ላለመቀበል ሞክረዋል። ዛሬ ያሉት ፕሮቴስታንቶችም እንደዚያው ለማድረግ ይሞክራሉ። እንደ እነርሱ አባባል ከሆነ ችግሩ ያለው ከእነርሱ ጋር የማይስማሙት ሌሎቹ ግለሰቦችም ሆኑ ቡድኖች መጽሐፍ ቅዱስን ሲያነቡ በትክክል ስለማያነቡት ነው ይላሉ።

ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስን በትክክል ለማንበብና በትክክለኛው መንገድ ለመረዳት ይሆናሉ ያሏቸውን የተለያዩ መፍትሔዎች "እነዚህ ናቸው፣ እነዚያ ናቸው" በማለት ትገ፤ የሚሏቸውን ነገሮች ከመጠቆም አላረፉም። ሆኖም የፕሮቴስታንቲዝምን ማብቂያ የለሽ የሆነ መከፋፈል የሚያስቆም መፍትሔ ግን ገና አላገኙም።

እስካሁን ድረስ የተሞከሩና የተለያዩ የፕሮቴስታንት ቡድኖች እንደ መፍትሔ የሚያቀርቧቸውን መርሆዎች ከዚህ ቀጥሎ እንመልከታቸው። እነዚህን በመከተል

ማንም ሰው መጽሐፍ ቅዱስን በራሱ አንብቦ በትክክል ለመረዳትና እውነትን ሁሉ ለማወቅ ይችላል ይላሉ። እነዚህም የሚከተሉት ናቸው፡-

**መርሕ 1፡- "መጽሐፍ ቅዱስ የሚያነብን ሰው መንፈስ ቅዱስ ይመራዋል፣ ስለዚህ አይሳሳትም።"**

"ማንኛውም ሰው መጽሐፍ ቅዱስን በራሱ መንገድ የመተርጎምና የመረዳት መብትም ችሎታም አለው፣ ሲተረጉምም መንፈስ ቅዱስ ይመራዋል፣ ስለዚህ አይሳሳትም"[55] የሚለው ይህ የፕሮቴስታንቲዝም ማዕከላዊ መሠረትና እምነት በተግባር ሲፈተሽ ምን ይመስላል? እንዲህ ከሆነ እንዲህ ብለው የሚያምኑት ፕሮቴስታንቶች ሁሉም መጽሐፍ ቅዱስን ሲረዱና ሲተረጉሙ አንዳችም ልዩነት የሌላቸው መሆን ነበረባቸው፣ ምክንያቱም መጽሐፍ ቅዱስ ተቃራኒ የሆኑ አስተምህሮዎችን ሊያስተምር አይችልምና። መንፈስ ቅዱስም ወደ አንድነት እንጂ ወደ መለያየት አይወስድምና። ሆኖም ግን ሁሉም "የእምነት መመሪያችን መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ ነው" የሚሉና እውነትን ይዘናል የሚሉ፣ ግን አንዳቸው ከሌላቸው የተለየ ትምህርት የሚያስተምሩ 40,000 የደረሱ የፕሮቴስታንት የእምነት ድርጅቶች በዓለማችን ላይ አሉ። ታዲያ ይህ ውጤት መጽሐፍ ቅዱስን ሲያነቡ መንፈስ ቅዱስ ቢመራቸው የተገኘ ውጤት ሊሆን ይችላልን?

ስለዚህ አንድ መጽሐፍ ቅዱስን እያነበቡ ይህን ያህል የእርስ በእርስ መለያየት ላይ መውደቃቸው "መጽሐፍ ቅዱስ የሚያነብን ሰው ሁሉ መንፈስ ቅዱስ ይመራዋል፣ ስለዚህ አይሳሳትም" የሚለውን መፍትሔያቸውን ከባድ ጥያቄ ምልክት ላይ ጥሎባቸዋል። በዚህ ሁኔታ መጽሐፍ ቅዱስን ማንም ሰው አንብቦ እውነተኛ ሐሳቡን ለመረዳት መንፈስ ቅዱስ ይመራዋል፣ አይሳሳትም" የሚለው ፕሮቴስታንቶች አቋም በተግባር ተፈትኖ የወደቀ ነው። የፕሮቴስታንቶች የመጽሐፍ ቅዱስ ትርጒም ራሱ ከመጀመሪያው ከጀመሩበት ጊዜ አንሥቶ በከፍተኛ ሁኔታ ተለውጧል።[56]

አንድ ሰው ለእምነቱ ታማኝ በሆነ መጠን ይህ ሁኔታ በፕሮቴስታንቲዝምና ከዚያ ውጭ ባሉ ክርስቲያኖች (በኦርቶዶክሳውያንና በካቶሊኮች) ዘንድ የሚያስከትለው ውጤት ተቃራኒ ነው። በኦርቶዶክሶችና በካቶሊኮች ዘንድ ይህ ሁኔታ፣ ማለትም አንድ ሰው በእምነቱ ጥብቅና እውነተኛ በሆነ መጠን የበለጠ አንድነትን ሲያጠናክር፣ በፕሮቴስታንት ዘንድ ግን መለያየትን ያስከትላል።[57] ምክንያቱም እርሱም መጽሐፍ

[55] Steve Bruce, *A House Divided*, pp. 34-35

[56] Steve Bruce, pp. 35.

[57] Steve Bruce, pp. 39.

ቅዱስን በራሱ አረዳድ ማንበብና መተርጎም ሲጀምር ያለበት ቡድን አረዳድ ላይጥመው ይችላልና፣ ያን ጊዜ ለመለየትና ሌላ አዲስ ቡድን ለመመሥረት ልቡ መሸፈት ይጀምራል። ይህ ደግሞ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው አስተምህሮ መሠረት የተፈቀደ ስለሆነ በራሱ ልክ የተሰፋ አዲስ ቡድን ይመሠርት ዘንድ እምነቱ የሚገፋው ይሆንበታል። ፕሮፌሰር ስቲቭ ብሩስ ጥልቅ በሆነው የሥነ ማኅበረሰብ ጥናቱ ይህን ሲያብራራ እንዲህ ይላል፡-

> የሮማ ካቶሊክ እና የኦርቶዶክስ ክርስቲያኖች ትውፊቶች፣ በየአብያተ ክርስቲያኖቻቸው ትውፊቶች ካላቸው እምነት የተነሣ፣ በአንጻራዊነት ደረጃ ከመለያየትና ከመከፋፈል ችግር የራቁና ያልተጋለጡ ናቸው። ሐዋርያዊ ቅብብሎሽ በሚባል ነገር የሚያምን ሰው ከቤተ ክርስቲያን ውጭ መዳን የሌለ መሆኑን ያምናል። ስለዚህም እውነተኛ አማኝ የሆነ ሰው ከቤተ ክርስቲያን ተለይቶ የሚወጣበት ሁኔታ ሩቅ ነው። ተለይተን እንውጣ የሚሉ የልዩነት አጀንዳ የሚያራምዱ እንቅስቃሴዎች ቢነሱ እንኳ ሰዎችን ከቤተ ክርስቲያን ተለይተው እንዲወጡና እነርሱን እንዲከተሏቸው ለማሳመን ከባድ የሆነ ፈተና ይሆንባቸዋል። . . .
>
> የካቶሊክ ወይም የኦርቶዶክስ አብያተ ክርስቲያንን ሁኔታ በትክክል ስንመለከተው መከፋፈል ጨርሶ አይኖርም ባይባልም ቅሉ የመሆን ዕድሉ ግን እጅግ በጣም ሩቅ ነው። በአንጻሩ ለፕሮቴስታንቶች ግን መከፋፈል በጣም ቀላል ነው። ብቸኛው የሥልጣን ምንጭ የሆነው መጽሐፍ ቅዱስ ለሁሉም አማኝ በእኩል ደረጃ ያለ ስለሆነ፣ አንደኛው ቡድን የእርሱን አረዳድ ትክክለኛው የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድ የእኔ ነው በማለት የሌላኛውን ቡድን አረዳድና አተረጓጎም ለመቃወም መንገዱ ምን ጊዜም ክፍት ነው። በጥብቅ እናምናለን የሚሉ ፕሮቴስታንቶች መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ ይተረጉማል ብለው ቢያምኑም፣ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ሌላ ምንም መረና የትምህርት ምንጭ የለም ብለው በሚያምኑ ግለሰቦችና ቡድኖች መካከል የተፈጠሩት የግጭት ታሪኮች ሲታዩ፣ ይህ እምነት የተለያዩና የሚቃረኑ የሆኑ አተረጓጎሞችን ሊፈታ የማይችል መሆኑን ግልጽ ያደርገዋል።[58]

ስለዚህ የፕሮቴስታንቶች ችግር ግለሰቦቹ በግላቸው መንፈሳዊነት የጎደላቸው መሆን አለመሆናቸው ሳይሆን ባሕርዩ ነው። መጀመሪያ ላይ ብዙዎቹ የፕሮቴስታንት እንቅስቃሴዎች በአንድነት አብረው የዘለቁት ለመሥራቹ ወይም ለመሥራቾቹ ስብእና

[58] Steve Bruce, p. 45 .

በነበራቸው ታማኝነት ነበር።[59] ሆኖም እነዚያ ግለሰቦች ሲያልፉ የፕሮቴስታንቲዝም ባሕርያዊ የሆነው ችግሩ ይወጣና እንደገና ይከፋፈላሉ። እንደዚህ እያለ ሂደቱ እንደቀጠለ ነው። ብሩስ ከጥናቱ በመነሣት፣ ከመከፋፈል በሽታ ሊጠበቅ የሚችለው "የእውቀት ምንጭ ግለሰቡ ነው" የሚለው ሳይሆን "ቤተ ክርስቲያን ናት" የሚለው መሆኑን ይገልጻል።[60] የፕሮቴስታንቲዝም ሁለንተናዊ ችግር ሥሩ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ይህ መጽሐፍ ቅዱሳዊ ያልሆነ ትምህርት ነው።

ይህ የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ የፈጠረው ሌላው ውጤቱ "ግለሰባዊነት - Subjectivism" ነው። ይህም ማለት ማንም ሰው በተረዳው መንገድ መተርጎም የሚችል ከሆነ እውነት አንዲትና አምላካዊ ሳትሆን ግለሰባዊና አንጻራዊ ናት ያሰኛል። ከዚህም የተነሣ በየጊዜው የሚፈጠሩ የፕሮቴስታንት ቡድኖች ከእነርሱ በፊት የነበሩትና እነርሱ የተገነጠሉባቸው ቡድኖች ይቀበሏቸው የነበሩትን መሠረታዊ የእምነት አንቀጾች ሳይቀር ወደ ጎን እየተዉ፣ ምንም ዓይነት መሠረታዊ አስተምህሮ ላይ ያልተመሠረተ ግለሰባዊ ስብስብ እየሆኑ ነው። ሁሉም የሚስማሙበትና እምነታቸው የሚቆምበት የጋራ አስተምህሮ ሊኖራቸው ባለመቻሉ፣ ዋናው ጉዳይ የምታምነው ነገር ምንድን ነው? የሚለው ሳይሆን "ዳግመኛ መወለድህ" (a "born again" experience) ነው ወደሚል ደረጃ ደርሰዋል። እንደዚሁም "በመንፈሳዊነት ለማደግ የሚረዳህን ነገር ሁሉ አድርግ" ወይም "እግዚአብሔር እየመራህ እንደሆነ ወደሚሰማህ ሂድ" ወይም "በልብህ ውስጥ ሰላም የሚሰጥህን ነገር አድርግ" ወደሚሉ ግላዊ ስሜቶች ወርዷል።

በካሪዝማቲክ ፕሮቴስታንት አንጃና በቅርንጫፎቹ ፓስተሮች ዘንድ ደግሞ "እግዚአብሔር እንዲህ ብሎ ተናገረኝ"፣ "መንፈስ ቅዱስ በልቤ ውስጥ እንዲህ እንድል ወይም እንዳደርግ አስረዳኝ"፣ "ጌታ በጆሮዬ ሹክ አለኝ"፣ "ይህን ነገር ስናገር ጌታ ምስክሬ ነው" ወደሚሉ መሠረታዊ ከሆነው ሐዋርያዊ የክርስትና አስተምህሮና እምነት ልዩ ወደሆኑ ግለሰባዊ ስሜቶችና ቅዠቶች ደረጃ ደርሰዋል። ይህ ሁሉ ውጥንቅጥ የሆነ ግለሰባዊ አካሄድ ፕሮቴስታንቲዝም ለዓለም አንድ የሆነውን እውነት ለመመስከር እንዳይችል አድርጎታል። "አ ዐቃቤ ስራይ ፈውስ ርእሰከ - ባለ መድኃኒት ሆይ መጀመሪያ ራስህን ፈውስ" የሚለው ቃልም ሊያሰናብተው አይችልምና። ሉቃ. 4፡23 መሠረታችን ነው ያሉት "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የፕሮቴስታንቲዝም መሠረቱ ሳይሆን መፍረሻው ሆነ። ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ብሎ የተነሣው ፕሮቴስታንቲዝም፣ ያከበረውና የተቆረቆረለት የመሰለውን መጽሐፍ ቅዱስን ተአማኒነቱን በከባድ አደጋ ላይ የጣለ ሆኗል።

[59] Steve Bruce, p. 45.

[60] "It should be obvious that only the Church is protection against schism."

በየዘመናቱ ከተፈጠሩትና እየተፈጠሩ ካሉት የፕሮቴስታንት ቡድኖች መካከል ለአብነት ያህል የተወሰኑትን እንመልከት።

**የተወሰኑ የፕሮቴስታንት ቡድኖች መሥራቾቻቸው፣ የተመሠረቱበት አገር እና ዓመት**

| | የአንጃው ስም | የመሥራቹ ግለሰብ ስም | የተመሠረተበት አገር | የተመሠረተበት ዓመት |
|---|---|---|---|---|
| 1. | ሉተራን | ማርቲን ሉተር | ጀርመን | 1517 |
| 2. | አንግሊካን ቤተ ክርስቲያን | ንጉሥ ሄንሪ 8ኛ | እንግሊዝ | 1534 |
| 3. | ሜኖናይት | ሜኖ ሲሞንስ | ሆላንድ | 1536 |
| 4. | ፕሪስባይቴሪያን | ጆን ኖክስ | ስኮትላንድ | 1560 |
| 5 | ኮንግሪጌሽናሊስት | ሮበርት ብራውን | ሆላንድ | 1582 |
| 6. | ባፕቲስት | ጆን ስሚዝ | ሆላንድ፣ አምስተርዳም | 1605 |
| 7. | ደች ሪፎርምድ ቸርች | ሚካኤሊስ ጆንስ | አሜሪካ፣ ኒው ዮርክ | 1628 |
| 8. | ኩዋከር | ጆርጅ ፎክስ | እንግሊዝ | 1652 |
| 9. | ኤጲስ ቆጶል (የአንግሊካል ቅርንጫፍ ዓይነት) | ሳኤል ሲቡሪ | አሜሪካ | 17ኛው መቶ ዓመት |
| 10. | አሚሽ | ጃኮብ አማን | ስዊዘርላንድ | 1693 |
| 11. | ሜቶዲስት | ጆን እና ቻርለስ ዊስሌይ (ወንድማማቾች) | እንግሊዝ | 1744 |
| 12. | ዩኒታሪያን | ቴዎፍሎ ሊንድሌይ | ለንደን፣ እንግሊዝ | 1774 |
| 13 | ሞርሞን | ጆሴፍ ስሚዝ | አሜሪካ | 1829 |
| 14. | ሰባተኛ ቀን አድቬንቲስት | ዊሊያም ሚለር እና ኤለን ዋይት | አሜሪካ | 1863 |

| | | | | |
|---|---|---|---|---|
| 15. | ሳልቬሽን አርሚ | ዊሊያም ቡዝ | ለንደን፣ እንግሊዝ | 1865 |
| 16. | ክርስቲያን ሳይንቲስት | ሜሪ ቤክር ኤዲ | አሜሪካ | 1879 |
| 17. | ጴንጤ ቆስጤ (ሙሉ ወንጌል) | ቻርለስ ፓርሃም | አሜሪካ | 1900 |

በአጠቃላይ ፕሮቴስታንት የሆኑ ሰዎች ሁሉ እምነቶቻቸውን የመሠረቷቸው ግለሰቦች ናቸው። መሥራቾቹ ሁሉም ምዕራባውያን ሰዎች ናቸው። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚል መርሕ ተነሥተው የፈጠሯቸው የየግለሰቦቹ ግለሰባዊ አረዳድ ውጤቶች ናቸው። ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ግን በራሱ በኢየሱስ ክርስቶስ በ34 ዓ. ም. በቀራንዮ ላይ የተመሠረተች ናት። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ሳትለወጥ አለች፣ ትኖራለችም። ማንም ይሁን ማን፣ የማንንም ግለሰብ አረዳድ ብቻውን ይዛ የምትነጉድ አይደለችም።

**መርሕ 2፡- "መጽሐፍ ቅዱስ የሚናገረውን ቃል በገጸ ምንባቡ ላይ እንዳለው ተረዳው፤ በቁሙ ውሰደው፤ ሌላ ትርጉም አያስፈልገውም።"** ("The Bible says what it means and means what it says")

ይህን መርሕ እነርሱ ይተገብሩታልን? መፍትሔስ ነውን?

ይህን ለመገንዘብ ይረዳን ዘንድ ለአብነት ያህል የሚከተሉትን የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች እንመልከት፡-

- "ኃጢአታቸውን ይቅር ያላችኋቸው ሁሉ ይቀርላቸዋል፤ የያዛችሁባቸው ተይዞባቸዋል አላቸው።" ዮሐ. 20፡23

ሉተርና ዝዊንግሊ ይህን ቃል እንዳለ በገጸ ንባቡ ወስደውታል ወይ? ብለን ስንጠይቅ መልሱ አልወሰዱትም ነው። ዝዊንግሊ "ኃጢአታቸውን ይቅር ያላችኋቸው ሁሉ ይቀርላቸዋል" የተባለው "ወንጌልን መስበክ ነው" ሲል ሉተር ደግሞ "እንደዚያ አይደለም" አለ። ታዲያ ጥሬ ቃሉን እንዳለ መውሰድ መፍትሔ ነው ካሉ፣ ለምን እነርሱ አልተጠቀሙበትም? ገጸ ንባቡ (ቃሉ) ላይ ወደሌለ፣ ነገር ግን እነርሱ መረዳታቸውን ወደሚገልጹበት ሌላ ትርጓሜ ለምን ገቡ? በዚህ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ላይ የተለያዩ ፕሮቴስታንት ቡድኖች ያላቸው አረዳድ የተለያየ ነው። ታዲያ "ቃሉን እንዳለ መውሰድ" መፍትሔ ከሆነ ለምን እነርሱ አይጠቀሙበትም? ለምን መፍትሔ አልሆናቸውም?

- "ይህ ሥጋዬ ነው።" ማቴ. 26፡26-28

ቅዱስ አንጻዮነው ሉተር እና ዝውንግሊ ግን ከመጀመሪያው ጀምሮ በዋናነት ያጣላቸው "ይህ ሥጋዬ ነው" የሚለው ቃል ምንነት ነበር። የተወዛገቡትም በንባቡ ቃል ሳይሆን በአተረጓጎሙ ነበር። በዚህ ቃል ላይ ምን ያክል እንደ ተወዛገቡና እንደ ተጣሉ እንዲሁም በየዘመኑ የተነሡ የፕሮቴስታንት የመጽሐፍ ቅዱስ ተርጓሚዎችና ሊቃውንቶች ነን ባዮች በየጊዜው የሚወዛገቡበት ጉዳይ መሆኑን ከላይ ተመልክተናል። ገጸ ንባቡን ብቻ መውሰድ በቂ ከሆነ፣ እነዚህ አካላት ሁሉም ቃሉን ይቀበላሉ፣ ክርክሩ መጽሐፍ ቅዱስን በማይቀበሉ ሰዎች መካከል የሚካሄድ አይደለምና። ቃሉ ያ[illegible] ውሰደው፣ ሌላ ትርጉም አያስፈልገውም" የሚሉት መርሓቸው መፍትሔ የሚሆን ከሆነ ለምን ተጣሉ?

- "ሰው ከውኃና ከመንፈስ ካልተወለደ በቀር ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ሊገባ አይችልም።" ዮሐ. 3፡5

በዚህ ቃል ላይ ያላቸው አረዳድ የተለያየ መሆኑን ከላይ ተመልክተናል። አሁንም የተለያዩት በጥሬ ቃሉ ሳይሆን በአተረጓጎሙ (በአረዳዱ) ላይ መሆኑ ግልጽ ነው።

- "ሴቶች በቤተ ክርስቲያን ራሳቸውን ይከናነቡ።" 1 ቆሮ. 11፡1-16

በዚህ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ላይ የፕሮቴስታንቶች አረዳድ የተለያየ ነው። በጣም ብዙ የፕሮቴስታንት ፓስተሮች ይህ ቃል "እንዳለ አይወሰድም" ይላሉ። ለምን? እንዳለ የማይወሰድ መሆኑን ማን ነገራቸው? እንዴትስ አወቁ? ገጸ ንባቡ እንደዚያ አይልምና! ስለዚህ ይህ መርሓቸውም የማይሠራ ነው።

**መርሕ 3፡- "ግልጽ ያልሆኑት የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች ግልጽ በሆኑት ይተረጎማሉ።"**

"ሙሉው መጽሐፍ ቅዱስ በአንድ መንፈስ ቅዱስ የተጻፈ እንደ መሆኑ፣ መጽሐፍ ቅዱስን ራሱ በራሱ ከመተርጎም የተሻለ ሌላ መንገድ ሊገኝ አይችልም"[61] ይላሉ። በሌላው የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍል ላይ በግልጽ በተጻፉትና በቀላሉ ለመረዳት በሚቻሉት ጥቅሶች መተርጎም ይቻላል ይላሉ። ይህ የሚሠራባቸው የተወሰኑ ሁኔታዎች መኖራቸው እውነት ነው። ሆኖም ግን ይህ ስልት ሁል ጊዜ ይሠራል ወይ? የሚለውን ጥያቄ እናንሣ፣ ተግባራዊ ውጤቱንም እንመልከት።

[61] George Mastrantonis, trans., Augsburg and Constantinople: the Correspondence between the Tübingen Theologians and Patriarch Jeremiah II of Constantinople on the Augsburg Confession, p.115.

ለምሳሌ አንድ ሰው ከዳነ በኋላ፥ ያን መዳኑን መልሶ ሊያጣው ይችላል? ወይስ አይችልም? በሚለው መሠረታዊ ጉዳይ ላይ በተቃራኒ ጎራ የቆሙ የፕሮቴስታንት አንጃዎች አሉ። አንዳንድ የፕሮቴስታንት ዲኖሚኔሽኖች እንዴ "ከዳንክ" ድነሃል፤ መዳንህን በምንም ዓይነት ሁኔታ ልታጣው አትችልም ይላሉ። ሌሎቹ ደግሞ መዳንን አግኝቶ የነበረ ክርስቲያን ከባድ ኃጢአት ከሠራ ያንን መዳኑን ሊያጣው ይችላል ይላሉ። ለዚህም በመጥምቃውያንን (Baptists) እና በሜቶዲስትች (Methodists) መካከል ያለውን ክርክር መመልከት በቂ ነው። መጥምቃውያን የሚባሉት የፕሮቴስታንት ቡድኖች፥ አንዴ የዳነ ክርስቲያን መዳኑን መልሶ ሊያጣ አይችልም ብለው የሚያምኑ ሲሆን፥ ሜቶዲስቶች ደግሞ ሰው ከዳነ በኋላ ፊቱን ከእግዚአብሔር ከመለሰ ያን ያገኘውን መዳኑን ሊያጣ ይችላል ባዮች ናቸው።

እነዚህ ሁለት ቡድኖች ይህን የተመለከቱ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶችን ግልጽነት በተመለከተ እንዴት እንደሚረዷቸው እንመልከት።

| የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል | **መጥምቃውያን (Baptists)**<br>**(አንዴ የዳነ ክርስቲያን መዳኑን መልሶ ሊያጣ አይችልም ብለው የሚያምኑት)** | **ሜቶዲስቶች (Methodists)**<br>**(ሰው ከዳነ በኋላም ፊቱን ከእግዚአብሔር ከመለሰ መዳኑን ሊያጣ ይችላል የሚሉት)** |
|---|---|---|
| "እግዚአብሔር በጸጋው ስጦታና በመጥራቱ አይጸጸትምና።" ሮሜ 11:29 | ግልጽ ቃል ነው። | ግልጽ ቃል አይደለም። |
| "በጎቼ ድምፄን ይሰማሉ . . . እኔም የዘላለም ሕይወትን እሰጣቸዋለሁ፥ ለዘላለምም አይጠፉም፥ ከእጄም ማንም አይነጥቃቸውም፡" ዮሐ. 10:27-28 | ግልጽ ቃል ነው። | ግልጽ ቃል አይደለም። |
| "ወደ እኔም የሚመጣውን ከቶ ወደ ውጭ አላወጣውም።" ዮሐ. 6:37 | ግልጽ ቃል ነው። | ግልጽ ቃል አይደለም። |
| "ጻድቁም ኃጢአት በሠራበት ቀን በጽድቁ በሕይወት አይኖርም።" ሕዝ. 33:12 | ግልጽ ቃል አይደለም። | ግልጽ ቃል ነው። |
| "ነገር ግን ለሌሎች ከሰበክሁ በኋላ ራሴ የተጣልሁ እንዳልሆን ሥጋዬን እየጎሰምሁ አስገዛዋለሁ።" 1 ቆሮ. 9:27 | ግልጽ ቃል አይደለም። | ግልጽ ቃል ነው። |

ይኸኛው የመፍትሔ ሐሳባቸው ትንሽ ተስፋ ሰጭ ቢመስልም በተጨባጭ ግን ለፕሮቴስታንት ቀውስና መከፋፈል ትርጉም ያለው መፍትሔ ሊያስገኝ አልቻለም። ይህ መፍትሔ ሊያልፈው ያልቻለው ዋናው ፈተና የትኞቹ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች "ግልጽ የሆኑ"፣ የትኞቹ ደግሞ "ግልጽ ያልሆኑ" መሆናቸውን መወሰን አለመቻሉ ነው። ምክንያቱም ቃሉ በራሱ "እኔ ግልጽ ነኝ" ወይም "አይደለሁም" አይልማ! ለአንደኛው "ግልጽ" የሆነው የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ለሌላኛው ደግሞ "ግልጽ ያልሆነ" ነው። ታዲያ "ግልጽ ያልሆኑት የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች ግልጽ በሆኑት ይተረጎማሉ" ሲሉ ግልጹ የትኛው ነው? ግልጽነቱስ ለማን ነው? ግልጽ መሆን አለመሆኑን የሚወስነውስ ማን ነው?

ከላይ ባለው ሰንጠረዥ እንደሚታየው ለመጥምቃውያን እነርሱ የያዙትን አቋም (እምነት) ይደግፋሉ ብለው የሚያምኑባቸው ጥቅሶች (ሮሜ 11፡29፣ ዮሐ. 10፡27-28፣ ዮሐ. 6፡37) ለእነርሱ "ግልጾች" ናቸው። ምክንያቱም እነርሱ የሚያምኑበትን አቋም የሚደግፉ ስለሚመስሏቸው ነው። ሆኖም እነዚያው ጥቅሶች ለሜቶዲስቶች ደግሞ "ግልጽ" አይደሉም። ምክንያቱ ደግሞ የያዙትን አቋም (እምነት) የማይደግፉ ሆነው ስላገኟቸው ብቻ ነው። ስለዚህ መጥምቃውያንና ሜቶዲስቶች ለእነርሱ ግልጽ የሆኑትን ጥቅሶች "ይሄ እንዴት ግልጽ አይሆንላችሁም?" እያሉ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶችን ይወራወራሉ፣ አንዱ በሌላው ይማረራሉ። ሁሉም ከያዙት አቋምና እምነት አንጻር ብይን በመስጠት "ግልጽ ነው" "ግልጽ አይደለም" ይላሉ እንጂ መጽሐፉ "ይህ ቃል ግልጽ ነው"፣ "ይህ ደግሞ ግልጽ አይደለም፣ ስለዚህ በሌላው ቃል መሠረት ተርጉሙት" አይልም። ስለሆነም ይህ መርሕ ቡድኖቹ በያዟቸው አስተምህሮዎች ላይ ተመሥርቶ የሚሰጥ ብይን እንጂ ራሱ የመጽሐፍ ቅዱሱ ቃል የሚበይነው ነገር ስላልሆነ ችግራቸውን አልፈታላቸውም፣ ሊፈታላቸውም አይችልም። ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስ ራሱን በራሱ ይተረጉማል፣ ወይም ግልጽ ያልሆነው ቃል ግልጽ በሆነው ቃል ይተረጎማል የሚለው ሐሳባቸው ስንዝር እንኳ የማያስኬድ ነው።

በአሜሪካ አገር ከ1780 እስከ 1830 የነበሩ የተለያዩ የፕሮቴስታንት ቡድኖች፣ እንቅስቃሴዎችና ግለሰቦች፣ ሁሉም በእያንዳንዳቸው "ከሰዎች ንክኪ ነጻ" የሆነውን ንጹሕ መጽሐፍ ቅዱሳዊ ክርስትና ለመመለስ ጥረት እያደረጉ መሆናቸውን ይናገሩ ነበር።[62] ለምሳሌም አሌክሳንደር ካምፕቤል የተባለው ፓስተር "መጽሐፍ ቅዱስን ልክ ከእኔ በፊት ሌላ ማንም ሰው እንዳላነበበው አድርጌ ለማንበብ ጥረት አድርጌያለሁ። ዛሬ ሳነባቸው ትናንትናና ከሳምንት በፊት እነርሱን ባነበብኩበት እሳቤና ሁኔታ ሆኜ እንዳላነብባቸው ከእኔው ከራሴ እንኳ በከፍተኛ ሁኔታ እጠነቀቃለሁ፣ ከእኔ ውጭ

[62] Nathan O. Hatch, *The Democratization of American Christianity*, 1989

ባለ በማንም ስም፣ ሥልጣን ወይም አሳቤ ተጽእኖ እንዲያሳርፍብኝም አልፈቅድም" ብሏል።[63]

ቻርለስ ቻውንሲ የተባለ (1727-1787) "ታዋቂ" ፕሮቴስታንት ፓስተር የነበረ ሲሆን መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ በራሴ አጥንቼ ከእውነተኛው የመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት ላይ እደርሳለሁ ብሎ ጀመረ። የራሴን የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት በጥልቀት አድርጌያለሁ ካለ በኋላ ደረስኩበት ያለው ድምድሜ መጽሐፍ ቅዱስ ዘለዓለማዊ ቅጣትን በተመለከተ የሚያስተምረውን ትምህርት ውድቅ በማድረግ "ሁሉም ሰው ይድናል" የሚል ነበር። ይህን ደረስኩበት ያለውን እውነት የጻፈበትን ጽሑፍ እርሱ ራሱም ለንትመት የበቃ ለመሆን "እጅግ በጣም አወዛጋቢ ነው" በማለት ችግሩን ተገንዝቦ ለ25 ዓመታት ሳይታተም ካቆየው በኋላ በሕይወቱ መጨረሻ አካባቢ ላይ "ከዘመናትና ከትውልዶች የተሰወረ ምስጢር" በሚል ርእስ አሳተመው። ጥቅስን ከጥቅስ ጋር የማነጻጸር ብዙና ረጂም የሆነ ዝርዝር በማሳየት የደረሰበት ድምዳሜ መጽሐፍ ቅዱሳዊ መሆኑን ለማሳየት ሞክሯል።[64]

በ19ኛው መቶ ዓመት ላይ በአሜሪካ አገር፣ አብዛኛዎቹ በቅድስት ሥላሴ የማያምኑና ራሽናሊስት የሚባሉ "ክርስቲያኖች"፣ "ከሐዋርያት ዘመን አንሥቶ የነበሩ የቤተ ክርስቲያን አባቶች መጽሐፍ ቅዱስን እንዴት ተረዱት?" ብሎ መጠየቅን በመቃወምና በኃይል በመንቀፍ፣ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን በብርቱ መስበክና መተግበር ቀጠሉ። ለምሳሌም ዩኒታሪያን የነበረው ኖኅ ዎርክስተር፣ እያንዳንዱ ሰው በቤተ ክርስቲያን ታሪክ ታላላቅ ስም ባላቸው ሰዎች ላይ ያላቸውን አክብሮት እርግፍ አድርገው ትተው ራሳቸው በራሳቸው ብቻ እንዲያነቡና እንዲረዱ አጥብቆ ይወተውት ነበር። "ቅዱሳት መጻሕፍት የተጻፉት ለመላው ሕዝብ በመሆኑ በሕዝቡ የመረዳት ዓቅም ልክ የተጻፉ ናቸው" ሲል ይናገር ነበር። ይኸው ሰው፣ እንደ ቅድስት ሥላሴ እና ይህን የመሰሉ መሠረታዊ የክርስትና እምነት ምስጢር የሚባሉ ነገሮች ሰዎች መጽሐፍ ቅዱስን ለራሳቸው ቢያነቡ ውድቅ ይደረጋሉ ይል ነበር።[65] የአሜሪካ ፕሮቴስታንት ፓስተሮች እንዲህ እያሉ አንዳቸው ከሌላቸው እየተቀባበሉ የየራሳቸውን ግላዊ መጽሐፍ ቅዱስን አጥንቼ የደረስኩበት እውነት በሚል ሰበብ ይገኛሉ። ይህም በኢየሱስ እየጫኑባቸው ምስኪኖች ላይ በሚከተሏቸው አረዳድ ክርስቶስ አምላክነት፣ በድንግልናዊ ልደቱና በትንሣኤው እንኳ አናምንም እስከ ማለት የሚደርሱ ክህደቶቻቸውን መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ አጥንቼ ጥቅስ ከጥቅስ አነጻጽሬ

---

[63] John L. Winebrenner, *History of All the Religious Denominations in the United States* p. 595.

[64] Edward M. Griffin, *Old Brick: Charles Chauncy of Boston*, pp. 109-25.

[65] Charles Beecher, *The Bible a Sufficient Creed*, pp. 24, 26.

የደረስኩበት እውነት እያሉ ይናገራሉ። የቤተ ክርስቲያን መሠረታዊ አስተምህሮን፣ ታሪክንና ሥርዐተ አምልኮን ሙሉ በሙሉ ውድቅ አድርገው፣ መጽሐፍ ቅዱስን ማጥናትን በራሳችን "ሀ" ብለን እንጀምራለን የሚለው አካሄዳቸው የሆነው፣ ይህን የታዘበ ጆን ኔቪን የተባለ ሰው "እያንዳንዱ ሰው በየራሱ መንገድ ይጠቀምበት ዘንድ ዕለቱን ከሰማይ ላይ የተበተነ መጽሐፍ አደረጉት"[66] ብሎ በምሬት እንደ ገለጸው ዓይነት ነው።

በተለይም ኔቪን፣ ዲኖሚኔሽኖችን ማቆሚያ በሌለው ሁኔታ በማባዛት ላይ ያለው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ የፈጠረውን ሁኔታ እንዲህ ሲል በአግራሞት ጠይቋል፡-

> ሁሉም መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ የሚል መርሕና መፈክር በቁርጠኛ ሁኔታ የሚያሰሙ፣ ነገር ግን እርስ በርሳቸው የሚጣሉ በጣም ብዙ የሆኑ ቸርቾችንና ቤተ እምነቶችን ስናገኝ ምን ብለን እናስብ? መጽሐፍ ቅዱስ ለሁሉም ሰው በጣም ግልጽ ከሆነና የክርስትና አስተምህሮንና ተግባራዊ ሕይወትን በተመለከተ ሁሉንም አሟልቶ የያዘ ከሆነ፣ ታዲያ ሰዎች መጽሐፍ ቅዱስን በነጻነት እንዲጠቀሙ በሆኑ መጠን፣ እና ይህን ለማድረግም ከተሰማሩባቸው የእውቀት ዘርፎች አንጻር የላቀ ትምህርትና አእምሮ ያላቸው በሆኑ መጠን፣ በሚያነቡት በመጽሐፍ ቅዱስ በጎ ተጽእኖ መሠረት በሃይማኖታዊ እምነታቸው ወደ አንድ ከመምጣት ይልቅ በቋሚነት አጽንተው አንዳቸው ከሌላቸው የሚለያዩ እንዴት ሊሆኑ ቻሉ?[67]

እንደዚሁም ይህ ሰው፣ ሰዎች መጽሐፍ ቅዱስን በራሳቸው አንብበው ይረዳሉ በሚለው እና ጥቂት ጠንካራ ግለሰቦች የራሳቸውን ሐሳብና ፈቃድ በሌሎች ላይ የሚጭኑባቸው የመሆኑን እውነታ በተመለከተም ጉዳዩን ከማስተዋሉ የተነሣ አስገርሞታል። ኔቪን እንዲህ ገልጾታል፡-

> ሲሰሟቸው ደስ የሚሉት - ነጻነት፣ ነጻ የሆነ እውነትን ፍለጋ፣ ግልጽ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት - የሚባሉት ቃላትና ሐረጎች "ሁሉንም ነጻ የሆነ አስተሳሰብን እና ሁሉንም ነጻ ሕይወትን የሚገድል" የሆነውን አዲስ ዓይነት "ቤተ ክርስቲያናዊ" አምባገነናዊ ገዢነትና ቅጥፈት የሸፈነ ጭምብል ነው።[68]

[66] John W. Nevin, *Early Christianity*, p. 255.
[67] John W. Nevin, *Antichrist; or, The spirit of sect and schism*, p. 137.
[68] John W. Nevin, p. 137.

በዚህ ሁኔታ መሬት ላይ በተግባር ያለውን እውነታ ሲያብራራም እንዲህ ብሏል፡-

> የዚያ አንጃ ነጻነት ያለው የራሱን መለያና የይለፍ ቃሎች የሆኑ ሐረጎችን ጮኾ በመናገር ላይ፣ የራሱን የመዝሙር ዓይነት በመዘመር ላይ፣ እና መጽሐፍ ቅዱስን በራሱ ነገረ ሃይማኖታዊ መነጽር በማንበብ ላይ ብቻ ነው። እነዚህና እነዚህን የመሳሰሉ ሌሎች ብዙ አጥሮች ያሉ በመሆናቸው በአንጃው ውስጥ ያሉት ተከታዮች በመጨረሻ የአንጃው መሪ በሚሆኑ ጥቂት ግለሰቦች አመራርና ገገርነት እጅ ላይ ይወድቃሉ። እነዚያም አባላቱን "ነጻ ናችሁ" እያሉ ነጻነታቸውን ግን እነርሱ ይወስዱና በላያቸው ላይ ገገርዎቻቸው ይሆኑባቸዋል።[69]

ሆኖም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን ሉተራዊ አስተምህሮ የሚከተሉ ግለሰቦችና ቡድኖች በመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶች ላይ የሚነሡ የአረዳድና የአተረጓጎም ልዩነቶች በራሱ በመጽሐፍ ቅዱስ ዳኝነት ይፈታሉ እየተባለ ይነገራቸዋል። የአረዳድና የአተረጓጎም ልዩነቶች በሌላ ዓይነት አረዳድና አተረጓጎም ሊፈቱ የሚችሉት እንዴት ብለው ነው? ወደ መጽሐፍ ቅዱስ የሚደረጉ ይግባኞች ሁሉም የመጽሐፍ ቅዱስ ገጸ ንባብ (ጥሬ ቃል) ይግባኞች ሳይሆኑ የአተረጓጎም ይግባኞች ናቸው። ስለዚህ እውነተኛው ጥያቄ "የማንን አተረጓጎም?" እንቀበል? የሚለው ነው።

መጽሐፍ ቅዱስን በተለያየ መንገድ የሚረዱና የሚተረጉሙ ግለሰቦችም ሆኑ ቡድኖች መጽሐፍ ቅዱስን ጠረጴዛ ላይ አስቀምጠው የአተረጓጎምና የአስተምህሮ ልዩነታቸውን እርሱ እንዲፈታላቸው ሊጠይቁት አይችሉም። መጽሐፉ አስማሚና ዳኛ ሆኖ ማገልገል ይችል ዘንድ በሆነ አካል መነበብና መተርጎም ይገባዋል። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው አስተምህሮ መሠረት ደግሞ ይህ አንባቢና ተርጓሚ አካል እያንዳንዱ ግለሰብ ነው፣ ስለዚህም በግለሰብ ተርጓሚዎች ቁጥር ልክ የሆነ ዳኛና በያኝ አለ ማለት ነው። ይህ ደግሞ አንድ እውነትና አንድ ሃይማኖት የሚለው መጽሐፍ ቅዱሳዊ አስተምህሮ ሳይሆን እውነት ግለሰባዊና አንጻራዊ ነው የሚለው የሰነፎች የስህተት አስተሳሰብ ነው። እነ ሉተር ሲነሡ የሮማ ካቶሊክ ቤተ ክርስቲያን ፖፕ ብቸኛውና የመጨረሻው የመጽሐፍ ቅዱስ ተርጓሚ ነኝ ማለቱን በመቃወም ተነሥተው ያንን በፓፓው የነቀፉትን ድርጊት ለእያንዳንዳቸው አደረጉት።

የፖፑን ብቸኛና የመጨረሻው የመጽሐፍ ቅዱስ የበላይ ተርጓሚነት ስህተት ውድቅ ማድረጋቸው ትክክል ነበር፣ ሆኖም ግን መጀመሪያ ላይ መሥራቾቹ ራሳቸውን፣

[69] John W. Nevin, p. 144.

በመሠረተ ሐሳቡ ግን ማንኛውንም ሰው ሌላ "ፖፕ" አድርገውት አረፉ።[70] የአንድ ፖፕን ብቸኛ ተርጓሚነት እንቃወማለን ብለው ራሳቸውን በፖፑ ቦታ በማድረግ ብዙ ፖፖችን ፈጠሩ። ለካቶሊክ ፖፕ ስህተት መፍትሔው ሌላ ስህተት አልነበረም። መፍትሔው ውጥንቅጡ የወጣ ሥርዓት አልበኝነትና መያዣ መጨበጫ የሌለው ግለሰባዊ አምባገነንነት አልነበረም። ግን ተሐድሶ ፕሮቴስታንት ያደረገው ይህን ነው።

## መርሕ 4፡- "ሂስቶሪካል - ክሪቲካል የአተረጓጎም ስልትን መከተል"

## (Historical-Critical Exegesis)

ግለሰባዊ በሆኑ የመጽሐፍ ቅዱስ አተረጓጎሞችና አስተያየቶች ባሕር ውስጥ የሰጠሙት ፕሮቴስታንቶች መለያየቶቻቸው እየጨመሩ እንጂ እየቀነሱ የማይሄዱ በመሆናቸው፣ ችግሩ ያሳሰባቸው የፕሮቴስታንት ምሁራን **ከዚህ** ሁኔታ ቢያወጣን ብለው ተስፋ ያደረጉት ስልት ሳይንስንና አመክንዮን (Science and reasoning) በመጽሐፍ ቅዱስ አተረጓጎማቸው ላይ ዋና መሣሪያ አድርጎ መጠቀምን ነው። ይህ ፕሮቴስታንቲዝምን እየተቆጣጠረውና እየወረሰው ያለው ስልት **"ሂስቶሪካል - ክሪቲካል የአተረጓጎም ስልት** (Historical-Critical Exegesis) ተብሎ የሚጠራው ነው። በአውሮፓ ዘመነ አብርሆት ሲጀምር ሳይንስ የሰው ልጆችን ችግሮች ሙሉ በሙሉ እንደሚፈታቸው ተደርጎ ከፍ ያለ እምነት ተጥሎበት ስለነበር፣ የፕሮቴስታንት ምሁራንም የሳይንስን የአጠናን ስልት በቴዎሎጂና በመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት ላይም መተግበር ጀመሩ።

ከዘመነ አብርሆት አንሥቶ የፕሮቴስታንት ምሁራን የመጽሐፍ ቅዱስን - ታሪኩን፣ ጥንታዊ የመጻሕፍት ቅጂዎችን፣ በመጀመሪያ የተጻፈባቸውን ቋንቋዎች፣ ወዘተ በኃይል መርምረዋል፣ አጥንተዋል። እነዚህ ምሁራን የሚያገኟቸውን ቅሬቶችና "አጥንቶች" ሁሉ ሳይንስ በደረሰበት ደረጃ ባፈራቸው መሣሪያዎች መርምረዋቸዋል። በእርግጥ በእነዚህ ምርምሮቻቸውና ጥናቶቻቸው በጣም ብዙ የሆኑ ጠቃሚ እውቀቶችና መረጃዎች የተገኙ መሆናቸው እውቅና ሊሰጠው የሚገባ ነገር ነው። ሆኖም ግን ይህ ስልት በጣም በከባድ ሁኔታ ብዙ ግዙፍና መሠረታዊ ስህተቶችንም ተሳስቷል። እንዲሁም "ሳይንሳዊ ነው" በሚለው የገነነ ስያሜ ተሸፋፍኖና ታሽጎ እርሱን አምነው የተከተሉትንና አሁንም እየተከተሉት ያሉትን ሰዎች ከመጽሐፍ ቅዱስ እውነታ ተቃራኒ ወደ ሆነ ሌላ አቅጣጫ መርቷቸዋል፣ እየመራቸውም ይገኛል። እንዲሁም "ሳይንሳዊ" በሚል ሽፋን እውነትን ብቻ የሚከተል ጤነኛና ገለልተኛ

[70] Steve Bruce, *A House Divided*, pp. 3-4.

ምርምር በመምሰል ውስጡን ለማያውቁት ሰዎች አማላይና ሳቢ ሆኖ ስለሚታያቸው ብዙ አላዋቂዎችን ወደ ገደል ወስዷቸዋል፤ አሁንም እየተወሰዱ ያሉም ብዙዎች ናቸው። እንደ ሌሎቹ የፕሮቴስታንቶች ስልቶችና የመፍትሔ መንገዶች ሁሉ ይህ ስልትም መጽሐፍ ቅዱስን ለመረዳት የሚሞክረው የቤተ ክርስቲያን ትውፊትን ውድቅ አድርጎ ነው። ዋናው መርሑ "መጽሐፍ ቅዱስ ራሱ ለራሱ ይናገር" የሚል ነው። በእውነት መጽሐፍ ቅዱስ ራሱ ለራሱ የሚናገር ከሆነ ይህን የሚጠላም ሆነ የሚቃወም እውነተኛ ክርስቲያን ሊኖር አይችልም። ችግሩ ግን ራሳቸውን በራሳቸው የመጽሐፍ ቅዱስ መናገሪያ እንደበት ወይም ቃል አቀባይ አድርገው የሚሾሙት ሰዎች መጽሐፉን የሚያዩበት መነጽር፣ ከዚያም "መጽሐፍ ቅዱስ እንዲህ ይላል" ብለው የሚናገሩት ነገር በራሳቸው ፕሮቴስታንታዊ እምነትና አስተሳሰብ መሠረት የተረዱትንና የመሰላቸውን እንጂ ራሱ መጽሐፍ ቅዱሱ የሚለውን አለመሆኑ ነው።

ገለልተኛና ምሁራዊ አጥኚዎች ነን ይበሉ እንጂ መጽሐፍ ቅዱስን የሚተረጉሙት በራሳቸው አስተምህሮ መሠረት ነው። ማንም ሰው ነገሮችን ሲያይና ሲያጠና በውስጡ ካለው ከእምነቱና ከአስተሳሰቡ ሙሉ በሙሉ ነጻ ሆኖ ሊያጠና የማይችል መሆኑ የታወቀ ነገር ነው (ጥናቱ ቁሳዊ ነገሮችን የተመለከተ እስካልሆነ ድረስ፤ ይህም እንኳ ሊያከራክር የሚችል መሆኑ እንዳለ ሆኖ)። ልክ በመስተዋት ፊት የቆመ ሰው የሚያየው ራሱን እንደሆነ ሁሉ፣ የፕሮቴስታንት ምሁራንም በመጽሐፍ ቅዱስ ላይ ብዙ ቢመራመሩና ቢጽፉም የጻፉት ግን ያው መልሰው የራሳቸውን እምነትና አስተምህሮ ነው።

እንደዚሁም የፕሮቴስታንት ምሁራን **ኢምፒሪሲዝም** (Empiricism) የተባለውን የሳይንስ የጥናት ስልት በቴዎሎጂና በመጽሐፍ ቅዱስ ጥናቶች ላይ እንተገብራለን በማለት መሠረታዊ የመርሕ ስህተትን ፈጽመዋል። ኢምፒሪሲዝም ማለት "ማንኛውም እውቀት ሁሉ በልምድ ላይ የተመሠረተ ነው" የሚል <u>እምነት</u> ነው። እንደዚሁም ኢምፒሪሲዝም "**በእርግጠኛነት ሊታወቁ የሚችሉት ነገሮች በሳይንሳዊ ምልከታ ሊረጋገጡ የሚችሉ ነገሮች ብቻ ናቸው፣ ከዚህ ውጭ በሳይንሳዊ ምልከታ ሊረጋገጡ የማይችሉ ነገሮችን በተመለከተ ግን ማወቅ አንችልም**" የሚል አስተሳሰብ ነው።[71]

እስኪ በመጀመሪያ ኢምፒሪሲስቶችን አንድ መሠረታዊ ጥያቄ እንጠይቃቸው። የእናንተ መሠረታዊ መርሕ፣ ማለትም - "በእርግጠኛነት ሊታወቁ የሚችሉት ነገሮች በሳይንሳዊ ምልከታ ሊረጋገጡ የሚችሉ ነገሮች ብቻ ናቸው፣ ከዚህ ውጭ በሳይንሳዊ ምልከታ ሊረጋገጡ የማይችሉ ነገሮችን በተመለከተ ማወቅ አንችልም" የሚለው

[71] S.H. Swinny; and Wolfhart Pannenburg, *Theology and Philosophy of Science*, p. 29.

ዐረፍተ ነገር ራሱ በሳይንሳዊ ምልከታ ሊረጋገጥ ይችላል ወይ? መልሱ ሊረጋገጥ አይችልም ነው! ምክንያቱም ይህ ዐረፍተ ነገር ሐሳብ እንጂ በማይክሮስኮፕም ሆነ በቴሌስኮፕ ሊታይ የሚችል ቁስ አካል አይደለምና።

ስለዚህ ይህ የኢምፒሪሲስቶች የህልውናቸው መሠረት የሆነው ዐረፍተ ነገር በሳይንሳዊ ምልከታ ሊረጋገጥ የማይችል ከሆነ፣ **"በሳይንሳዊ ምልከታ ያልተረጋገጠ ነገር ሊታወቅና እውነት ነው ሊባል አይቻልም"** የሚለው የራሳቸው የመነሻ አቋማቸው እውነት አይደለም ማለት ነው። ሌላውን ነገር በተመለከተ በሳይንሳዊ ምልከታ ማረጋገጥ አለብን ብለው የተነሡ ሰዎች የራሳቸውን ሐሳብ በሳይንሳዊ ምልከታ ያላረጋገጡ ከሆነ፣ ራሳቸው ያልተገበሩትንና ያላከበሩትን መርሕ በሌላው ላይ እንተገብራለን ለማለት እንዴት ይችላሉ?

ስለዚህ ኢምፒሪሲስቶች ሁሉም ነገር በሳይንሳዊ ምልከታ ካልተረጋገጠ ሊታወቅ አይችልም ብለው ሲያበቁ የእነርሱው የራሳቸው ሐሳብ ግን በሳይንሳዊ ምልከታ ሊረጋገጥ የማይችል ነው! ስለዚህ ይህ መነሻ ዐረፍተ ነገራቸው ትክክል ከሆነ ራሱን በራሱ የሚያጠፋ ይሆናል ማለት ነው። በሌላ በኩል ደግሞ አይ፣ ቢያንስ ይህ ዐረፍተ ነገራችን በሳይንሳዊ ምልከታ መረጋገጥ ሳያስፈልገው በራሱ እውነት ነው የሚሉ ከሆነ፣ **አንደኛ** ራሳቸው ያሉትን ሕግ ገና ከመነሻው አፈረሱት ማለት ነው፤ ስለዚህ አቋማቸው ስህተት ነው ማለት ነው። **ሁለተኛ** ደግሞ ይህ ለእነርሱ አቋምና እምነት ሲሆን የሚሠራ ከሆነ፣ ለሌላው አካል አቋምና እምነትስ ለምን አይሠራም? ስለዚህ የኢምፒሪሲስቶች መሠረት እንዲህ መሠረት አልባ ነው።

ይህ የኢምፒሪሲዝም መሠረተ እሳቤ ፈራሽነቱ እንዳለ ሆኖ፣ የአቋማቸውን ምንነትና በመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድ ላይ የሚያመጣውን ውጤት ትንሽ ገፋ አድርገን እንመልከተው። "ሳይንሳዊ" የሚሉትን የምርምር ስልት በቅዱሳት መጻሕፍት ጥናት ላይ መተግበር አለብን የሚለው ነገራቸው ዋናው ስህተቱ በዚህ ስልት ሊጠኑ ለሚችሉ ነገሮች የሚሠሩ የሙከራዎችንና የምልከታዎችን የጥናት ስልት (Empirical assumptions) በቅዱሳት መጻሕፍት፣ በታሪክ እና በቴዎሎጂ ጥናት ላይም እንዳለ እንተገብራለን ማለታቸው ነው። በመመልከትና በሙከራ (Observation and Experimentation) የጥናት ስልት እውቀትን ለማግኘት የሚደረጉ ምርምሮች በአግባቡና ሁነኛ በሆነ ሁኔታ ሊሠሩ የሚችሉት በተፈጥሮ ሳይንስ መስኮች ላይ ሲተገበሩ ነው። ሆኖም ሊሠሩ በማይችሉባቸው ላይ፣ ለምሳሌ በታሪክ ውስጥ አንድ ጊዜ ብቻ የተፈጸሙና ያልተደገሙ፣ ሊደገሙም የማይችሉ ድርጊቶችና ኩነቶች ላይ፣ ወይም በሙከራ ሊጠኑ የማይችሉ ነገሮች ላይ ይህን የጥናት ስልት እንተግብረው ብንል ትርጉም ያለው ውጤት ሊያስገኝ አይችልም።

የእግዚአብሔር ቃልን ከድንግል ማርያም በድንግልና መፀነሱንና መወለዱን፣ ሞትን ድል አድርጎ መነሣቱንና ማረጉን፤ እና ይህን የመሰሉ ነገሮችን በዚህ የጥናት ስልት መሠረት እውነትነታቸውን ማረጋገጥ የሚቻለው እነዚህን የመሰለን ድርጊት በማየትና በማጥናት ነው። ሆኖም እነዚህ ክስተቶች በታሪክ ውስጥ አንዴ ብቻ የተፈጸሙና የማይደገሙ በመሆናቸው በዚህ ስልት የሚያጠኑት "ምሁራን" ይህን የመሰሉ ነገሮችን በድጋሚ የማየት ዕድል ስለማይኖራቸው፤ መጽሐፍ ቅዱስ እንደዚህ ያሉ አምላካዊ ልዩ ኩነቶችንና ተአምሮችን ሲናገር እነርሱ "ተረት" ወይም "አፈ ታሪክ" ናቸው ብለው ይደመድማሉ። ገና ከመጀመሪያው ይዘውት የሚነሡት እምነት (ነገሮች መደገም መቻል አለባቸው የሚለው) እንደዚህ ዓይነት ነገር እንዳይቀበሉ አድርጓቸዋልና ነገሩ ተፈጽሞ የነበረ ቢሆንም ባይሆንም እነርሱ የሚደመድሙት "የለም ማለት ነው" ብለው ነው።[72] አንድ ነገር ለመኖሩ ማስረጃ አለማግኘት ነገሩ ላለመኖሩ ማስረጃ አይደለም እንደሚባለው (Absence of evidence is not evidence of absence) ነው። ችግሩ ይዘውት የተነሡት የእምነታቸው ችግር ነው። ማንኛውም ነገር መደጋገምና መታየት መቻል አለበት የሚለው የራሳቸው እምነት እንጂ የተረጋገጠ ሳይንሳዊ እውነት አይደለምና። ነገሮች መሆን ያለባቸው በዚህ መልክ ብቻ መሆኑን ያረጋገጠ ሳይንስ የለምና! ስለሆነም የራሳቸው መርሕ እስረኞች ናቸው።

ስለ ክርስትና አስተምህሮ እውቀት የሚገኘው በዚህ የጥናት ስልት መሠረት ከሆነ፤ ሳይንቲስቶች ወደ ዓለመ መናፍስት ዘልቆ የሚገባና መላእክት ስለመኖር አለመኖራቸው መመርመር የሚችል መሣሪያ መሥራት አለባቸው ማለት ነው። እንደዚህ ሆኖም ብዙ የፕሮቴስታንት ምሁራን አጋንንትና ዲያብሎስ የሚባሉ ነገሮች የሌሉ መሆናቸው በሳይንስ ተረጋግጧል እያሉ ነው።[73] ዲያብሎስ በእነርሱ ፊት ቆሞ ፎቶ መነሣት ወይም ቪዲዮ መቀረጽ ነበረበት ማለት ነው? ዲያብሎስም ሆነ ሠራዊቱ አጋንንት በኢምፒሪሲስቶች ፊት ቀይና ደማቅ ልብስ ተጎናጽፈው ቢቆሙ እንኳ፤ ክስተቱን ከያዙት ቁስ አካላዊ ከሆነው እምነት ጋር ተስማሚ በሆነ መንገድ ይገልጹታል እንጂ አጋንንት አሉ አይሉም።

እንደዚህ ያሉት ሰዎች "ነጻ አሳቢዎች" ነን በማለት ራሳቸውን ቢያወድሱም ቅሉ እንደ እምነት ከያዙት አስተሳሰብ ጋር የማይስማማን ማንኛውንም ነገር ላለመቀበል አስቀድመው የዘጉ ናቸው።[74] ስለዚህ የሚቀበሉት ሊቀበሉት የሚፈልጉትን ብቻ ነው፤ ያ ደግሞ ከመጀመሪያውኑ በያዙት እምነት (አቋም) ላይ፤ ማለትም ማንኛውም ነገር መታየትና መጠናት መቻል አለበት በሚለው ላይ የተመሠረተ ነው። ስለዚህ

---

[72] G. E. Michalson, Jr., *Pannenburg on the Resurrection and Historical Method*, pp.345-359.

[73] Rev. Robert T. Osborn, *Faith as Personal Knowledge*, pp.101-126.

[74] እንደ ላይኛው

ከእነርሱ እምነት ውጭ የሆነ ሌላ ነገር ወይም ክስተት ቢኖር እንኳ ያን ለመቀበል አእምሯቸውን አስቀድመው ስለዘጉ አይቀበሉትም። እነዚህ በነጻ አሳቢ ስም ያሉ ጭፍኖች ናቸው።

የፕሮቴስታንቶች የመጽሐፍ ቅዱስ የትርጓሜ ስልት ነኝ እንደሚለው በእውነት ሳይንሳዊ ቢሆን ኖሮ፣ የሚደርስባቸው ውጤቶችም ወጥ በሆኑ ነበር። ሆኖም ፕሮቴስታንቶች በተጨባጭ ያሉበትን ሁኔታ ስናይ ግን ከዚህ በተቃራኒው ሆኖ እናገኘዋለን። የፕሮቴስታንቶች መጽሐፍ ቅዱሳዊ ጥናትና ውጤት በቀውስ ውስጥ መሆኑን ራሳቸው የፕሮቴስታንት ምሁራን እየገለጹ ናቸው። ታዋቂ ፕሮቴስታንትና የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት ጥናት ምሁር ነው የሚሉት ጌርሃድ ሃስል እንዲህ ብሏል፦

> በ1970ዎቹ ውስጥ 5 አዳዲስ ዓይነት የብሉይ ኪዳን የቴዎሎጂ አስተሳሰቦች ተፈጥረዋል፤ ሆኖም በጥናት ዘዴም ሆነ በአካሄድ ከእነዚህ አንዳቸውም ከሌላቸው ጋር አይስማሙም።[75]

በዚህ "ሂስቶሪካል - ክሪቲካል የአተረጓጎም ስልት" - (Historical-Critical Exegesis) በተባለው ስልት መጽሐፍ ቅዱስን አጥንተን በውስጡ ያለውን እውነት እናገኛለን፣ ከዚያም መጽሐፍ ቅዱስ ስለ ራሱ ሲናገር እንሰማዋለን የሚሉት የፕሮቴስታንት ምሁራን አሁን የደረሱበት የምሁርነት ደረጃ በማንኛውም የመጽሐፍ ቅዱስ ጉዳይ ላይ እነርሱ ከሚፈልጓቸው ዓይነት ድምዳሜዎች ላይ ለመድረስና እነዚያን "ሳይንሳዊ" ብለው በማሞካሸት "አዲስ" ሐሳባቸውን ለመደገፍና ለመናኘት ጥሩ ስኮላርሺፕ ማግኘት ከሚችሉበት ደረጃ ላይ ደርሰዋል። "ይህን ሳይንሳዊ የጥናት ስልት ተጠቀምን" በማለት፣ በማንኛውም ጉዳይ ላይ ከሚፈልጉት ድምዳሜ ላይ መድረስ ይችላሉ። ይህ እንደ ሒሳብ ወይም ፊዚክስና ኬሚስትሪ ያለ ሳይንስ ስላልሆነ እንደዚህ ለማድረግ ክፍት ነው። "ሳይንስ ነኝ" ይበል እንጂ "ስመ ሳይንስ - pseudo science" ነው። ስመ ሳይንስ ነው የሚባልበትም ምክንያት፣ እግዚአብሔርንና የእርሱን ሐሳብ የያዙትን ቅዱሳት መጻሕፍት በዚህ መንገድ ማጥናትና ቁሳዊ ነገሮችን ስናጠና እንደምናገኘው ያለ ወጥና ተመሳሳይ የሆነ አተረጓጎም ማግኘት ፈጽሞ የሚቻል ስላልሆነ ነው።

በዚህ ስም የሚነገረው የመጽሐፍ ቅዱስ ትርጓሜ አጥኚዎቹ ይዘውት ከተነሡት ቅድመ እምነት ጋር የሚስማማውን አተረጓጎም በመጽሐፍ ቅዱስ ላይ መጫን ወይም ማላከክ ብቻ ነው። "ሳይንሳዊ" በሚል ካባ የተደበቀው የፕሮቴስታንቶች የመጽሐፍ ቅዱስ የትርጓሜ ምርምርና ጥናት ውጤቱ የራሳቸው የፕሮቴስታንት

75 Gerhard Hasel, *Old Testament Theology: Basic Issues in the Current Debate*, p. 9.

ምሁራት ቱዎሎጂያዊና ፍልስፍናዊ እምነቶች ውጤትና ባሪያ ብቻ ነው እንጂ የእውነተኛ ምርምርና ጥናት ውጤት አይደለም።[76]

የፕሮቴስታንት ምሁራን በተግባር እያደረጉ ያሉት የእነርሱን አጀንዳ የሚስማሙ ቁጥሮችንና ማስረጃዎችን በጥንቃቄ ይመርጡና የሚደርሱባቸው ድምዳሜዎቻቸው አስቀድመው የተወሰኑና የታወቁ እንደመሆናቸው የእነርሱን የጥናት ዘዴ በመጽሐፍ ቅዱስ ላይ ወደ መተግበር ይሄዳሉ። ከዚያም ከራሳቸው ቅድመ እምነት ጋር የሚስማሙ ነገሮችን "እውነተኛ የመጽሐፍ ቅዱስ ትርጓሜ አገኘን" ብለው እንደ አዲስ ግኝት ይጽፋሉ።[77] እነዚህ ምሁራን በመጽሐፍ ቅዱስ አስተምህሮ ላይ "አዳዲስ የፈጠራ ቲዎሪዎች" በመፍጠር ተግባር ላይ በከፍተኛ ፉክክር ላይ ይገኛሉ።

ይህ ደግሞ የኑፋቄ ዋናው ባሕርይ ነው፤ አዲስነት፣ ዕብሪት፣ ግላዊ አስተያየት፣ እና ራስን ማታለል - እነዚህ ሁሉም ኑፋቄ ተፀንሶ የሚወለድባቸውና የሚያድግባቸው ምቹ መሬቶቹ ናቸው። በዚህ መንገድ የተጓዙ የፕሮቴስታንት ምሁራን ሄደው ሄደው መሠረታዊ የሆኑ የክርስትና አስተምህሮዎችን አንቀበልም እስከ ማለት ደርሰዋል። ለምሳሌም በእንግሊዝ አገር በተደረገ ጥናት 50% የሚሆኑት የአንግሊካን ፓስተሮች፣ ኢየሱስ ክርስቶስ ከቅድስት ድንግል ማርያም በድንግልና መወለዱን አናምንም ብለዋል። 30% የሚሆኑት ደግሞ የጌታችንን ትንሣኤ አናምንም ብለዋል፣ 20% የሚሆኑት ደግሞ እርግጠኞች አይደለንም ብለዋል።[78]

**ፕሮቴስታንቶች እዚህ ላይ የሚያነሡት ጥያቄ፡-**

> "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሮ የሚቃወሙ ቡድኖችም በእነርሱ ውስጥ መጽሐፍ ቅዱሳዊ በሆኑ ጉዳዮች ላይ ልዩነቶችና አለመግባባቶች አሉባቸው። በኦሬንታል ኦርቶዶክሶች፣ በምሥራቅ ኦርቶዶክሶች፣ እና በካቶሊኮች ዘንድ በውስጣቸው እርስ በእርሳቸው የማይግባቡባቸው ጉዳዮች አሏቸው። ስለዚህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን የሚቃወሙ አካላትም
>
> "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው ትምህርት እንደሚመሩት ሁሉ፣ እነርሱም በውስጣቸው ብዙ ልዩነቶች አሉባቸው። ስለዚህ እኛም ሆን እነርሱ በእኩል ሁኔታ ላይ ነን። በመሆኑም እነርሱም ከእኛ የተሻሉ ስላልሆኑ በዚህ ረገድ እኛን ሊወቅሱን አይችሉም።"

---

[76] Thomas Oden, *Agenda for Theology: After Modernity What?*, pp 103-147.

[77] እንደ ላይኛው

[78] Frank Schaeffer, *Defending Orthodoxy (Against Protestantism)*, video.

መልስ፡-

ይህ እኛ በማንለውና ባላልነው የቀረበ ትችት (strawman) ነው። ስለሆነም አቅጣጫውን የሳተ ጥያቄ ወይም ወቀሳ ነው። ምክንያቱም እኛ የምንለው "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሯቸው ትክክል ቢሆን ኖሮ በዚህ እምነት የሚያምኑት ሁሉም አንድ ዓይነት እምነት ሊኖራቸው ይገባ ነበር ነው። እኛም ሆን ሌሎቹ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው የማያምኑ አካላት ግን ለምን አንድ እንዲሆኑ ይጠበቅባቸዋል? ምክንያቱም ከመጀመሪያውም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ በማንበብ ወደ አንድ ዓይነት እምነት መድረስ ስለማይቻል በቤተ ክርስቲያን መርሐ እምነትና ትውፊት መሠረት መረዳት ይገባል ባዮች እስከሆኑ ድረስ፣ በማያምኑበት መርሕ ለምን ይመዘኑበታል? ከጥንቱም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ የሃይማኖት አንድነትን አያመጣም ብለዋልና።

የሌሎቹን ለራሳቸው እንተውላቸውና ኦርቶዶክሳውያን ቤተ ክርስቲያናዊ እንጂ ግለሰባዊ አረዳድና እምነት ስለሌላቸው፣ ከቤተ ክርስቲያናዊው አስተምህሮ የወጣና የተለየ የሆነ ነገር የሚያመጣ ካለ ችግሩ የራሱ እንጂ የቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ ያመጣው አይደለም። በፕሮቴስታንቶች ግን ማንም ሰው አንዱ ከሌላው የተለየ አረዳድና አስተምህሮ ይዞ ቢነሣ ሁሉም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ባዮች ስለሆኑ መለያየታቸው የአስተምህሯቸው ውጤት ነው። ስለዚህ ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን በዚህ ረገድ የምትወቀስበት ወይም በፕሮቴስታንቶች ውስጥ ካለው ሽህ ዓይነት መለያየት ጋር የምትደረብበት አንዳችም ምክንያት የለም።

ከዚህም ባሻገር ዋናው ነገር በኦርቶዶክሳውያን ዘንድ መሠረታዊ በሆኑ ጉዳዮች ላይ አንዳችም መለያየት የለም። በመዳን ምንነት ላይ፣ አንድ ሰው የሚድነው እንዴት ነው? በሚለው ላይ፣ በምስጢረ ጥምቀት ላይ፣ በምስጢረ ቊርባን ላይ፣ በንስሐ ላይ፣ በክህነት ላይ፣ እነዚህን በመሳሰሉት መሠረታዊ ነገረ ሃይማኖታዊ አስተምህሮዎች (ዶክትሪን) ላይ አንዳችም ልዩነት የላቸውም። ሆኖም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚሉ በፕሮቴስታንቶች ዘንድ ግን እንደዚህ ማለት አይችሉም። ከላይ እንደ ተመለከትነው መሠረታዊ በሆኑ ነገረ ሃይማኖታዊ ጉዳዮች ላይ የአንዱ ቡድን አቋም ከሌላው የተለየ ነው። ስለዚህ ፕሮቴስታንቶች ኦርቶዶክሳውያንን እንደዚህ ለማለት የሚያበቃ አንዳችም መነሻ የላቸውም።

በዚያውም ላይ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሮ የምንቃወመው መጽሐፍ ቅዱሳዊ ባለመሆኑ እንጂ በኋላ ያስከተለውን ውጤት ካየን በኋላ አይደለም፣ ይህ የኋለኛው የመሠረታዊው ስህተት ውጤት ነውና። ዋናው ችግሩ ያለው አስተምህሮው

ላይ ነው! ምን አስከተለ? የሚለው ከዚያ በኋላ የመጣ ነው። ግን ውጤቱም የማንነቱ ማጎዪያ ነው።

እንደዚሁም ኦርቶዶክሳውያን የሥርዐተ አምልኳችን ይዘትና ሂደት ወጥነት ያለው ነው። የሥርዓተ አምልኳችን ዋናው ማጠንጠኛ ምስጢረ ቁርባን ስለሆነ ጸሎተ ቅዳሴያችን በሚገርም ሁኔታ ወጥና ከአጥቢያ አጥቢያ ወይም ከአገር አገር የማይለያይ ነው። ኢትዮጵያ ውስጥ ያለ አንድ የኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን አሜሪካ አገር ካለ ሌላ የኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ጋር ጸሎተ ቅዳሴውና ሥርዐቱ ልዩነት የለውም። በፕሮቴስታንቶች ዘንድ ግን እንደዚህ አይደለም። በየሳምንቱ እሑድ የሚኖራቸው "አምልኮ" በአብዛኛው የሚወሰነው በፓስተሩ "ዝግጅት" እና ስሜት፣ እና ሚስቱ በምታዘጋጀው "መዝሙር" ነው።[79] እንኳን ከአገር አገር ይቅርና በአዲስ አበባ ውስጥ ያሉና ሁሉም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚሉ አምስት የፕሮቴስታንት ቸርቾች በአንድ ቀን ቢጎበኙ "አምልኳቸው" የተለያየ ነው። እንደዚህ የሆኑበት ምክንያቱ ደግሞ ቋሚ የሆነ ሥርዐተ አምልኮ የሌላቸው ስለሆኑ ነው። ይልቁንም "ጌታን በገባህ መጠን ግለጠው"፣ "ደስ ባለህ መንገድ አመስግን"፣ ወዘተ በሚባሉ ልቅነትንና እንደ ራስ ስሜት መሆንን በሚያበረታቱ ስብከቶች የታገዘ ነው እንጂ። የኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ግን የዕለቱ ሥርዓተ አምልኮ ብቻ ሳይሆን የወርኃዊውም፣ የዓመታዊውም የታወቀ ነው።

በአንድ በሆነ ቀን፣ ለምሳሌ በጥቅምት 27 ቀን የሚቆመው ማኅሌት ከመነሻው እስከ መድረሻው፣ የዚያ ቀን የዕለቱ ብቻ ሳይሆን አስቀድሞ የዋዜማው ቀለም በሙሉ፣ ድንቅ በሆነ ሁኔታ የተቀመረ ነው። ከመጽሐፍ ቅዱስ የሚነበቡት መጻሕፍትና ምንባባት እስከ ምዕራፋቸውና ቁጥራቸው መነሻና መድረሻ ድረስ የተለኩና የታወቁ ናቸው። ሁሉም የተቀመረ ብቻ እንዳይሆንና ዕለቱን በተመለከተ በአዲስ ምስጋና ማመስገን ይቻል ዘንድ ደግሞ ቤቱና ልኬቱ በታወቀ ሁኔታ ቅኔዎችን መቀኘት እንዲቻል ሆኖ የተሠራ ነው። ስለዚህ በዋዜማው ቅኔዎች አሉ፣ በዕለቱ ደግሞ ድርገት ሲወርድ ክብር ይእቲ የተባለ የጌታን ሕማሙንና ነገረ መስቀሉን ብቻ በተመለከተ የሚደረግ ቅኔ አለ። ከዚያም ዕለቱንና ከዚያም አለፍ ያሉ ጉዳዮችን ለመዳሰስ የሚያስችል ዕጣነ ሞገር የተባለ ቅኔ ይቀኛሉ። መሠረትን መጠበቅን ከአዲስነት፣ አዲስነትን ከሥርዓት ጋር ያዋሐደ ድንቅ ሥርዓተ አምልኮ ነው። ፕሮቴስታንቶች ከዚህ ከምኑ ይደርሱና ነው "እኩል ነን" ለማለት የሚደፍሩት? በየት ታልፎ?

እንደዚሁም ክርስቲያናዊ ሥነ ምግባርን በተመለከተም በኦርቶዶክሳውያን ዘንድ ኃጢአትና ጽድቅ የሚባሉት መሠረታዊ ነገሮች ወጥ በሆነ ሁኔታ የታወቁ

[79] ፍራንክ ሻፈር፡ አንድ የቪዲዮ ገለጻ ላይ ያቀረበው።

ናቸው እንጂ እንደ ፕሮቴስታንቶቹ ለየግለሰቡ ግላዊ ብያኔ የተተው አይደሉም። በኦርቶዶክሳውያን ዘንድ ግብረ ሰዶማዊነት ኃጢአት ነው፣ ውርጃ ኃጢአት ነው፣ ዝሙት ኃጢአት ነው፣ ስግብግብነት ኃጢአት ነው፣ . . .። በፕሮቴስታንቶች ዘንድ ግን ግብረ ሰዶማዊነት ኃጢአት ነው ወይስ አይደለም? በሚለው ላይ፣ ውርጃ ትክክል ነው አይደለም? በሚለው ላይ፣ እና ይህንና ይህን በመሰሉ መሠረታዊ ጉዳዮች ላይ እንኳ አንድ ዓይነት አቋም የላቸውም። በመሠረታዊ የክርስትና አስተምህሮና ሥነ ምግባራዊ ጉዳዮች ላይ እንኳ እንደየ ግለሰቡ የተለያየ አመለካከት ነው ያላቸው። ስለዚህ በዚህ ጉዳይ ላይ ራሳቸውን ከኦርቶዶክሳውያን ጋር ለማወዳደርና "እነርሱም እንደ እኛ ናቸው" ለማለት ያሉበት ሁኔታ ፈጽሞ አይፈቅድላቸውም።

## 1.9 ሶላ ስክሪፕቱራ ያስከተለው ውጤት እና የሉተርና የካልቪን

### አጸፋዊ ምላሽ

ገና ከመጀመሪያው፣ ፕሮቴስታንቲዝም ሁለት ዓይነት እርስ በርሳቸው የሚቀናቀኑ ትውፊቶችን ፈጠረ። አንደኛው የሮማ ካቶሊክ ቤተ ክርስቲያንን በማደስ በእርሷ ላይ ተመሥርተን እንሥራ የሚል ሲሆን፣ ሌላኛው ደግሞ ሁሉንም ነገር በማጥፋት ላይ የተመሠረተው የአናባፕቲስቶችና ኋላም ኩዋከሮችና እነርሱን የመሰሉ በመቶዎች የሚቆጠሩ አንጃዎች የተከተሉት አካሄድ ነበር። እነዚህኞቹ ቡድኖች ማንኛውንም ነባራዊነት ያለው ነገር ሁሉ የሚቃወሙ፣ ማኅበራዊ ውሎችንና ሐላፊነቶችን ሳይቀር፣ መንግሥታዊ አስተዳደርንም ሁሉ የሚቃወሙ ነበሩ። ለአናባፕቲስቶች፣ ኢየሱስ ክርስቶስ፣ ምስጢራት የሚከወኑባትና የድኅነት ጸጋን የምትሰጥ ቤተ ክርስቲያንን የመሠረተ ሳይሆን፣ ለእነርሱ "ታላቁ ነጻ አውጭ"፣ የምን ጊዜም ሌኒን ወይም ማኦ ዓይነት ሰው ነው።

አናባፕቲስቶች "ክርስቲያናዊ ፍቅር" በሚል ስም ብዙ ሴት ማግባትን ይፈቅዱ ነበር። ከተማዎችን እየወረሩ በዚያ የሚገኙ የአበዳሪና ተበዳሪ መዝገቦችን በማጥፋት ጋርዮሻዊ አኗኗርን ለማስፋፋት ይሰብኩና ይሞክሩ ነበር።[80] "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው መርሕ በጥብቅ ተግባር ላይ እንዲውል በአጽንኦት ይታገሉ ነበር። ከዚህም ጋር ብዙ ሁከትና ብጥብጥ መፍጠራቸውን አጥብቀው ተያይዘውት ነበር። የአናባፕቲስቶች አብዮታዊ አካሄድ ከፈጠረው ሁኔታ የተነሣ፣ ሉተርና ካልቪን፣ እንዲሁም ሌሎቹም የመጀመሪያው የተሐድሶ አራማጆች መጀመሪያ ላይ ያደርጓቸው የነበሩትን አብዮታዊ የነበረውን ንግግራቸውንና አካሄዳቸውን ማለዘብና ማጠፍ ጀመሩ። አንድ ወቅት ካልቪን በነገሥታትና በጦጦች ላይ አመጽ እንዲቀሰቀስ

[80] Frank Schaeffer, *Dancing Alone*, p.107.

ዘመን ጊዜ፤ ሌሎቹ ፕሮቴስታንቶች ነገሮች ባሉበት ሁኔታ ተጠብቀው እንዲቀጥሉና እመድ እንዲደቀስቀስ ለምንሰው ነበር። ፕሮቴስታንቶች አንዴ የጀመሩት ተሐድሶ በየጊዜው ምን ያህል መለያየትን እየፈጠረ መሆኑን በተረዱ ጊዜ፤ ቢያንስ ሌሎች ተጨማሪ መለያየቶችን ለማስቀረት በማሰብ የተለያዩ የእምነት መግለጫዎችንና ስምምነቶችን ለማጽደቅና ሰዎችን በእነዚያ ሥር ተሰባስበው በአንድነት እንዲኖሩ ለማድረግ ሞክረዋል። ለምሳሌም የኦፍስበርግ ኮንፌሽን ለአናባፕቲስቶች አጸፋ የተዘጋጀ የእምነት አንቀጽ ነበር።

ሆኖም ተሐድሶዎቹ ሥርዓትና አግባብ አስፈላጊም ጠቃሚም ስለመሆኑ የተረዱት በጣም ዘግይተው ነበር። ስለዚህም ሉተርና ካልቪን፤ አናባፕቲስቶች ልክ እንደ እነርሱ መጽሐፍ ቅዱስን ብቻ እንከተላለን እያሉ የሚፈጥሯቸው ማኅበራዊ፤ መንፈሳዊና ሁለንተናዊ ምስቅልቅሎች ከመጠን በላይ ሲሆኑባቸው ኃይልን ወደ መጠቀም ሄዱ። ሉተር በ1538 አናባፕቲስት የሆነ ማንም ቢሆን በሞት እንዲቀጣ የሚለውን አዋጅ ፈረመ።[81] ፕሮቴስታንቶች እነርሱ የሮማን ቤተ ክርስቲያን ሲነቅፉበት የነበረውን ጭካኔና የኃይል ርምጃ እነርሱም በተጠናከረና በበለጠ ሁኔታ ተጠቀሙበት። መጽሐፍ ቅዱስንና ነገረ ሃይማኖትን እንዲህ ነው ብላ የምትመራ አንዲት ቤተ ክርስቲያን በሌለችበትና ሁሉም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚል መርሕ እየተመራ "ትክክለኛው እኔ ነኝ" እያለ በሚሹኽበት የፕሮቴስታንት ዓለም ዘንድ መለያየት መለያየትን፤ መከፋፈል መከፋፈልን እየወለደ ዛሬ ድረስ እንደ ቀጠለ ነው።

የጀመሩት የተሳሳተ የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድ መንገድ ያስከተለውን ችግር የተመለከተው ካልቪን የእርሱን አተረጓጎም የማይቀበሉ ሰዎች እየበዙ ሲሄዱ ባየ ጊዜ የዚህ መፍትሔው መጽሐፍ ቅዱስን የሚተረጉሙ በከፍተኛ ደረጃ የተማሩ አገልጋዮች ሲኖሩ ነው አለ። ስለዚህም ካልቪን "መጽሐፍ ቅዱስን መተርጎም የሚገባው እንደዚህ ነው" እያለ ነባራዊውን ትውፊት በራሱ ትውፊት መተካት አስፈለገው። ለዚህ ይረዳው ዘንድም ካልቪን ከተከታዮቹ ጋር በመሆን መጽሐፍ ቅዱስ ላይ የእርሱን አስተምህሮና አረዳድ በኅንና በኅን የያዘ "መጽሐፍ ቅዱስ" አዘጋጀ። ካልቪንና ተከታዮቹ መጽሐፍ ቅዱስን ሲያስተምሩ ንጹሕ ቃሉን እንዳለ የሚያስተምሩ ሳይሆን ጥቅሱን ይጠቅሱና የሚተረጉሙትና የሚያስተምሩት ግን በኅንና በኅን በተቀመጠው የካልቪን አተረጓጎም መሠረት ነበር። ይህም የራሳቸው የሆነ ካልቪናዊ "ትውፊት" መፍጠራቸው ነበር።

ሉተርም እንዲሁ የእርሱን አስተምህሮ በሚቃወሙት ላይ ኃይል ወደ መጠቀም ወረደ። የተሐድሶዎቹ መሥራቾች ሉተርና ካልቪን የሮማ ካቶሊክን ተቃውመውና

[81] E. Digby Baltzell, *Puritan Boston and Quaker Philadelphia*, p. 61

ጀምረው በኋላ ወደ ኃይልና ብለው እናስተምራለን ወንጌል የሆነ ንጹሕ ፍጹም ሰው ያመጸ ላይ በትውፊት በሥርዓትና ስንመለከት፣ ማሸግሸግ ፈላጭ ቆራጭነት ወደ ሥርዓት" "አዲስ ማቆምና ወደ ትውፊት" "አዲስ የራሱን መልሶ እንደገና ግልጽ የሆነ ማሳያ ለመሆኑ የሚደርስ ግጭት ወደ ይህንኑ መሥራት እንደሚሄድና ብለው የጀመሩት ተርጉመው ተረዳው መንገድ በገባህ ራስህ ነው። መጽሐፍ ቅዱስን ሲፈጥር አልበኛነትን ሥርዓት ውጥንቅጥንና አስተምህሯቸው ሉተርና ካልቪን ይህ ትውፊት" ፈጠሩ። "ተሐድሷዊ አዲስ ሲመለከቱ ሰዎች ይከተሉት ዘንድ

ሉተርና ካልቪን እነርሱው ጭረው ያቀጣጠሉት እሳት መልሶ ራሳቸውን ያቃጥላቸው ጀመር። ራሳቸው ትውፊትና ሥርዓት አያስፈልግም ብለው ጀምረው ሲያበቁ ይህን መርሕ የተገበሩ አናባፕቲስቶች ነገሩን ሁሉ ግልብጥብጥ እያደረጉ ባስቸገሯቸው ጊዜ አናባፕቲስቶችን ለመቋቋም ሲሉ የራሳቸውን ትውፊት ፈጠሩ።[82]

ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነን ማንኛውም ትውፊትና ቃል ሁሉ እናጠፋለን ብለው የተነሡት ፕሮቴስታንቶች ራሳቸው በመጽሐፍ ቅዱስም ሆነ በቅዱስ ትውፊት የማይገኙ፣ "የሁሉም አማኞች የሁለት ጊዜ መወለድ ኅብረት" ("twice-born fellowship of all believers")[83]፣ "የግል አዳኝ"፣ የሚሉ ቃላቶችንና ሐረጎችን በመጠቀም ክርስትናን ምድራዊ (ሴኩላር) የማድረግ ጉዟቸውን ቀጠሉ። ለመጽሐፍ ቅዱሳዊ አረዳድ መሪና መሠረት የነበረውን ሐዋርያዊውን ቅዱስ ትውፊት (Apostolic Tradition) ግለሰባዊ በሆኑ ስሜቶቻቸውና አረዳዶቻቸው ተኩት። "ቅድስት ቤተ ክርስቲያን የምታምነውና የምታስተምረው ከጥንት ጀምሮ እንደዚህ ነው" የሚለውን ጥንታዊ የእምነት አገላለጽ፣ "እኔ የማምነው እንደዚህ ነው" በሚል ግለሰባዊ አቋም ይለውጡት ጀመር። የማይናወጥና የማይለወጥ የሆነው ነገረ ሃይማኖታዊ እውነት ቀርቶ የውስጥ ስሜትና ግላዊ መረዳት ብቻ እንዳሻቸው የሚናኙበት ሆነ።

በዚህም ፕሮቴስታንቲዝም ማንም ሰው ለእርሱ የሚመቸውን ሃይማኖት እንዲፈጥር መንገዱን አመቻቸ። ማንም ሰው ለራሱ ማመን የሚፈልገውን ሐሳብ "እኔ መጽሐፍ ቅዱስን የተረዳሁት እንደዚህ ነው" በሚል ይፈጥራል። ያም ባይሆን ከብዙ ሺህ ዓይነት የፕሮቴስታንት ቡድኖች መካከል አማርጦና አወዳድሮ ለእርሱ ስሜትና ፍላጎት ደስ የሚለውን "መግዛት" ይችላል። ጥቂት ቆይቶ ያ ይስማማኛል ብሎ ወስዶት የነበረው የፕሮቴስታንት የሃይማኖት ቡድን እንደ ጠበቀው የሚመቸው ሆኖ ካላገኘውም "በነጻ" መቀየር ይችላል። ፕሮቴስታንቲዝም እንደ ሸቀጥ ገበያው ሁሉ በእምነት ገበያም እጅግ በጣም ሰፊ የሆነ አማራጭ በማቅረብ እምነትን መቀለጃ

[82] Frank Schaeffer, *Dancing Alone*, p.110

[83] Frank Schaeffer, *Dancing Alone*, p.114

አድርጓታል። በዚህ ሂደትም ፕሮቴስታንቲዝም ሴኩላሪዝምን ፀንሶ ወልዷል።[84]

በዚህም መሠረታዊ የሆኑትን የክርስትና እውነቶች - የኢየሱስ ክርስቶስን የባሕርይ አምላክነቱን፣ በድንግልና መወለዱን፣ ከሙታን መነሣቱን፣ ሳይቀር መካድና እነዚህን ማመን የግድ አይደለም ከሚሉ አቋሞች የደረሱ ብዙዎች ናቸው። ሊበራል ፕሮቴስታንቶች ደግሞ ሴቶችንና ግብረ ሰዶማውያንን በይፋ "ካህን" ማድረግን፣ ውርጃን ተገቢ ነው ማለትን፣ ከዘመኑ ጾታዊ ፖለቲካ አንጻር ሁሉን አቀፍ ይሆን ዘንድ መጽሐፍ ቅዱስን እንዲያርሙና እንዲያስተካክሉ ለሴቶች ይህን ሥልጣን መስጠትን በአደባባይ እያደረጉ ናቸው። ምናልባት የተሐድሶ መሥራቾቹ ሉተር ወይም ዝዊንግሊ ወይም ካልቪን ከመቃብር ቢነሡና እነርሱ በጀመሩት የተሐድሶ ፕሮቴስታንት እምነት ስም እየሆኑ ያሉት ነገሮች እጅግ በጣም ርቀው መሄዳቸውን በመግለጽ ተቃውሞ ቢያቀርቡ እንኳ፣ የዘመኑ ምዕራባዊ ፕሮቴስታንት ኤጲስቆጳል "ካህን" ወይም ፕሪስባይቴሪያን ግብረ ሰዶማዊ "ፓስተር" እርሱ የተወሰኑ የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍሎችን እነርሱ ከተረጎሙበት በተለየ የተረዳቸውና የተረጎማቸው መሆኑንና ይህም ደግሞ መብቱ መሆኑን በኩራት ሊመልስላቸው ይችላል። ምን ጊዜም ግለሰባዊ አረዳድና አተረጓጎም እስከሆነ ድረስ፣ ሉተርና ግብረ ሰዶማዊው "ፓስተር" አንዳቸውም እኔ ብቻ ትክክል ነኝ ብለው መሟገት አይችሉም። የሃይማኖትን ግለሰባዊነት፣ "ሁሉም ሃይማኖት ትክክል ነው" የሚለውን አንጻራዊነት፣ እና የሴኪዩላሪዝምን መንፈስ የፈጠረው የእነ ሉተር "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የተሳሳተ መነሻ ነው።

መጽሐፍ ቅዱስን በራሴ አረዳድ እተረጉማለሁ ብለው የተነሡ ፕሮቴስታንቶች ማለት የሚችሉት፣ "በእኔ አረዳድ መሠረት መጽሐፍ ቅዱስ እንዲህ ይላል"፣ ወይም "ጥናቶች እንደዚህ ያሳያሉ" የሚሉ ግላዊ አመለካከቶችን ብቻ ነው። በዚህም ፕሮቴስታንቶች ራሳቸው በራሳቸው የራሳቸውን ህልውና አጠፉ፣ ፕሮቴስታንት የራሱን መቃብር ቆፍሮ ራሱን የቀበረ ሆነ።[85] ፕሮቴስታንቶች "ነፍስ መዝራታቸውን" የተረዱት ብዙም ሳይቆዩ ነበር። ሉተር እንኳ ይላቸዋል ሊባሉ የሚያስቸግሩ ጫፍ የወጡ ትምህርቶችንና እብደቶችን የያዙ አንጃዎች በየጊዜው መፈልፈላቸው የዕለት ተዕለት ክስተት ሆነ።

[84] Steve Bruce, *A House Divided*, p. 23, pp. 229-30.
[85] Steve Bruce, *A House Divided*, p. 73-74

## 1.10 መጽሐፍ ቅዱስ እንዴት ይተርጎም (እንዴት እንረዳው)?

መጽሐፍ ቅዱስን የሚያነብብ ሰው ሐሳቡን ይረዳ ዘንድ ካስፈለገ በማንበብ ብቻ ማቆም ሳይሆን ወደ መረዳት መሄድ ያለበት መሆኑን፣ አረዳድ ደግሞ ትርጓሜ መሆኑን ከላይ አይተናል። ፕሮቴስታንቶች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ሲሉም መጽሐፍ ቅዱስን አንብበን እናቁም ማለታቸው ሳይሆን መጽሐፍ ቅዱስን የሚያነብብ ሰው ሁሉ ሐሳቡን ለመረዳትና ለመተርጎም ብቁ ነው ማለታቸው መሆኑንም እንዲሁ አይተናል። ስለዚህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው ጉዳይ ላይ ያለው መሠረታዊው ነጥብ፣ **መጽሐፍ ቅዱስን ማን ይተርጉመው?** የሚለው ጉዳይ ነው። ይህም ማለት ፕሮቴስታንቶች እንደሚሉት መጽሐፍ ቅዱስን እያንዳንዱ ሰው በየግሉ አረዳድ ይተርጉመው? ወይስ ሌላ መንገድ አለ? የሚለው ነው።

ከሐዋርያት ዘመን አንሥቶ የነበሩ ክርስቲያኖች መጽሐፍ ቅዱስን የሚረዱትና የሚተረጉሙት እንዴት ነበር? ራሱ መጽሐፍ ቅዱስስ ማንም የሚያነበኝ ሰው ሁሉ በራሱ አረዳድ ይተርጉመኝ ይላልን? ወይስ ሌላ የሚለው ነገር አለ? የሚሉትን ነጥቦች ማየት አስፈላጊ ነው።

### 1.10.1 መጽሐፍ ቅዱስ ግለሰባዊ ትርጉምን በተመለከተ (Private or Personal Interpretation) ምን ይላል?

1. **በግል መተርጎም እንደማይገባ ያስጠነቅቃል።**
   ሐዋርያው ቅዱስ ጴጥሮስ በመልእክቱ ላይ እንዲህ ይላል፡-

> ይህን በመጀመሪያ እወቁ፤ በመጽሐፍ ያለውን ትንቢት ሁሉ፣ **ማንም ለገዛ ራሱ ሊተረጉም አልተፈቀደም።** 2 ጴጥ. 1:20-21

እንግዲህ ይህ ቃል በግልጽ የሚናገረው፣ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያለውን የትንቢት ቃል ማንም ሰው በራሱ አረዳድ ሊተረጉመው ያልተፈቀደ መሆኑን ነው። "በመጽሐፍ ያለውን ትንቢት" ሲል መላውን መጽሐፍ ቅዱስን ማለቱ ነው፣ ምክንያቱም በመጽሐፍ ቅዱስ ያለው ወይ ትንቢት አለያም የትንቢት ፍጻሜ (ወንጌል) ስለሆነ ነው። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያለውን ቃል ማንም ሰው "እኔ እንደ ገባኝ"፣ "እንደ እኔ አረዳድ" እያለ በግሉ ሊተረጉም "አልተፈቀደም" ብሎ **መጽሐፍ ቅዱስ** በግል **ሊተረጎም እንደማይገባው** በጽኑ ቃል አስጠንቅቋል። ታዲያ መጽሐፍ ቅዱስ ከዚህ በላይ በምን ዓይነት አገላለጽና ቃል ሊናገር ይገባው ነበር ይሆን?

መንፈስ ቅዱስ ወንጌልን ያስተምረው ዘንድ ፊልጶስን የላከለት ኢትዮጵያዊው ጃንደረባ የተናገረው ቃልም እጅግ የሚገርም ነው፤ እንዲህ ይላል፡-

> ፊልጶስም ሮጦ የነቢዩን የኢሳይያስን መጽሐፍ ሲያነብ ሰማና፡- **በውኑ የምታነበውን ታስተውለዋለህን**? አለው። እርሱም፡- **የሚመራኝ ሳይኖር ይህ እንዴት ይቻለኛል**? አለው። . . . ጃንደረባውም ለፊልጶስ መልሶ፡- እባክህ፤ ነቢዩ ይህን ስለ ማን ይናገራል? ስለ ራሱ ነውን ወይስ ስለ ሌላ? አለው። . . . የሐዋ. 8፡26-39

ይህ የኢትዮጵያዊው ታላቅ ሰው መልስ መጽሐፍ ቅዱስን ማንበብ ብቻውን የክርስትናን አስተምህሮ ለማወቅ በቂ አለመሆኑን ያረጋግጥልናል። ቃሉን የሚያነቡትና የሚሰሙት ሰዎች የቃሉን ሐሳብ በትክክል ይረዱት ዘንድ የሚተረጉምላቸው ሰው የሚያስፈልጋቸው መሆኑን በግልጽ የሚናገር ነው። መጽሐፍ ቅዱስን ማንበብ ብቻ በቂ ቢሆን ኖሮ፣ ይህ ኢትዮጵያዊ ጃንደረባ ከኢሳይያስ ትንቢት ሲያነብብ የነበረውን ቃል ምን ማለት መሆኑን የማይረዳ ባልሆነ ነበር። መጽሐፍ ቅዱስን የሚያነብ ማንኛውም ሰው በራሱ ለመረዳትና ለመተርጎም ብቁ ቢሆን ኖሮ፣ እንደ ዛሬው በአስፋልት መንገድ ላይ በመኪና ወይም በአውሮፕላን እየተጓዘ ሳይሆን በሠረገላ ላይ እየተጓዘ እንኳ የእግዚአብሔርን ቃል የማንበብ ጥልቅ ፍቅር ከነበረው ከዚህ ታላቅ ኢትዮጵያዊ የተሻለ ማን ይኖር ነበር?

ቅዱስ ፊልጶስ "በውኑ የምታነበውን ታስተውለዋለህን?" ብሎ በጠየቀው ጊዜ፣ "ካነበብኩ ለምን አይገባኝም?" የሚል የትዕቢት መልስ አልመለሰለትም። ይልቁንም "እባክህ፤ ነቢዩ ይህን ስለ ማን ይናገራል? ስለ ራሱ ነውን ወይስ ስለ ሌላ?" ብሎ ጠየቀው እንጂ። ከዚያ በኋላም ፊልጶስ "አፉን ከፈተ፤ ከዚህም መጽሐፍ ጀምሮ ስለ ኢየሱስ ወንጌልን ሰበከለት።" እያነበበው የነበረውን ቃል ተረጎመለት፣ እርሱም ተረዳ። ከዚያ በኋላ ነበር በመንገድ ሲሄዱ ወደ ውኃ በደረሱ ጊዜ "እነሆ ውኃ፤ እንዳልጠመቅ የሚከለክለኝ ምንድር ነው?" ብሎ የጠየቀው። ወደዚህ መዳን ለመድረስ መጽሐፉን ይዞ ማንበብ ብቻ ሳይሆን፣ የሚያነቡትን እኔ ራሴ ለመረዳት ብቁ ነኝ በሚል ትዕቢትም ሳይሆን፣ እንደ ፊልጶስ በመንፈስ ቅዱስ የተጠሩና የተላኩ ቅዱሳን ሐዋርያትና በእነርሱ እግር የተተኩ አባቶቻችን በተረዱበትና በተረጎሙበት መንገድ መረዳት የግድ ነው። ከዚህ ውጭ እኔው ራሴ አንብቤ ይገባኛል እያሉ በግል አረዳድ መንጎድ በፕሮቴስታንቶች የደረሰባቸውን አለማየት ነው።

ወንጌል አሳስባችኋለሁ፤ **እኔ ደግሞ የተቀበልሁትን**
ቅዱስ ጳውሎስ "ወንድሞች ሆይ፤ የሰበክሁላችሁን . . .
**ከሁሉ በፊት አሳልፌ ሰጠኋችሁ"** በማለት ለቆሮንቶስ ክርስቲያኖች የሰጣቸው (የጻፈላቸውና

በቃሉ ያስተማራቸው) "የተቀበለውን" እንጂ የራሱን ግላዊ አረዳድ አለመሆኑን ጽፏል። 1 ቆሮ. 15፡1-3 እንደዚሁም ማንም ሰው ቢሆን መጽሐፍ ቅዱስን የሚረዳውና የሚናገረው እርሱ በመሰለውና ደስ ባለው መንገድ አይደለምና በኤፌሶን መልእክቱ ላይ እንዲህ ብሏል፡- "ስለ ወንጌልም . . . መናገር እንደሚገባኝ ስለ እርሱ በግልጥ እናገር ዘንድ ለምኑ።" ኤፌ. 6፡20 ቅዱስ ጳውሎስ ይናገር የነበረው "መናገር እንደ ቻለው" ወይም "መናገር እንደ ፈለገው" ሳይሆን "መናገር እንደሚገባው" ነበር። ይህ ይሆንለት ዘንድም "ስለ እኔ ለምኑ" አለ። ታዲያ ግላዊ የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድና አተረጓጎም የሚል ነገር ከየት መጣ? መጽሐፍ ቅዱስን እንዲጽፉ ይህ ታላቅ ጸጋ የተሰጣቸው ቅዱሳን ሐዋርያት እንኳ ይህን ያህል ከተጠነቀቁ፣ እንደ ግሌ አረዳድ እተረጉመዋለሁ ለማለት መድፈር የሚችል ማን ነው?

ቅዱስ ጳውሎስ በገላትያ መልእክቱ ላይ የተናገረው ነገር ደግሞ እጅግ የሚገርም ሆኖ እናገኘዋለን። ይህም እንዲህ የሚል ነው፡-

> እንደ ተገለጠልኝም ወጣሁ፤ **ምናልባትም በከንቱ እንዳልሮጥ ወይም በከንቱ ሮጬ እንዳልሆን** በአሕዛብ መካከል **የምሰብከውን ወንጌል አስታወቅኋቸው**። ገላ. 2፡2

ቅዱስ ጳውሎስ ጌታችን ጌታችን ካረገ በኋላ ቆይቶ የተጠራና ከ12ቱ ሐዋርያት ጋር አብሮ ያልነበረ በመሆኑ ከተጠራና ለተወሰነ ጊዜ ከሰበከ በኋላ፣ እያስተማረው ያለው ትምህርት ጌታችን ለሐዋርያት ካስተማራቸው ትምህርት ጋር ሙሉ በሙሉ አንድ መሆኑንና ምናልባትም ሲያስተምር ያጎደለው ወይም የጨመረው ነገር እንዳይኖር ለማረጋገጥ በማሰብ የሚያስተምረውን ትምህርት ይገልጥላቸው ዘንድ ሐዋርያት ወደ ነበሩበት ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ። "ምናልባትም በከንቱ እንዳልሮጥ ወይም በከንቱ ሮጬ እንዳልሆን በአሕዛብ መካከል የምሰብከውን ወንጌል አስታወቅኋቸው" ያለው ለዚህ ነው። ታዲያ ቅዱስ ጳውሎስ እንኳ የሚሰብከው ወንጌል ምናልባት ትንሽ እንኳ የአስተምህሮ ስህተት እንዳይኖርበት ያን ያህል ከተጠነቀቀ፣ እኔው ራሴ በገባኝ መሠረት እተረጉማለሁ አስተምራለሁ ለማለት የሚደፍር ማን ነው?

ይኸው ሐዋርያ በመጀመሪያው ሐዋርያዊ ጉዞው ወንጌልን እየሰበከ ሳለ፣ ቢጽ ሐሳውያን (Judaizers) የተሰኙ አካላት ስለ ግዝረትና ስለ መሳሰሉት ጉዳዮች ውዝግብ በፈጠሩበት ጊዜም ያን ሃይማኖታዊ ጉዳይ በጉባኤ አስወሰነ እንጂ በራሱ አረዳድና ሥልጣን ተመሥርቶ አልወሰነም። የሐዋ. 15፡2-6 ታዲያ ቅዱስ ጳውሎስ እንኳ በሐዋርያት ጉባኤ ላይ የተወሰነውን እንጂ በራሱ በግሉ የነበረውን አረዳድ ይዞ በራሴ እመራለሁ ያለ ካልሆነ፣ የራሱን የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል አረዳድ እንደ መጨረሻ እውነት አድርጌ እወስዳለሁ ለማለት የሚደፍር ማን ይሆን? ዛሬስ ስንቱ

ወገኖችን የራሱን አረዳድና ስሜት በየአዳራሹ ሲናገር ወንጌልን የሰበከ እየሰመሰለው "በከንቱ እየሮጠ" ይሆን?

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ማለት በተግባር ሲታይ "እኔ ብቻ" እንደ ማለት ነው። ምክንያቱም የምትቀበለው የአንተን የግልህን አረዳድ ብቻ ከሆነ የምትቀበለውና የምታምነው ራስህን ብቻ ነው ማለት ነው። ማንኛውም አስተምህሮ የሚለካውና የሚመዘነው በአንተ ግላዊ አረዳድ ከሆነ ፍጻሜው የሚሆነው ግላዊነትና አንጻራዊነት ነው። ምክንያቱም በዚህ አስተምህሮ የሚያምንና እርሱን የሚተገብር ሌላውም ሰው የራሱ አረዳድና አተረጓጎም ስለሚኖረው፣ ይህ አረዳድና አተረጓጎም ደግሞ ለሰውዬው እውነተኛው እርሱ ስለሆነ፣ ሁሉም ሰው በጋራ የሚቀበለው አንድ የሆነ እውነት አይኖርም ማለት ነው። በአንጻሩ የሚኖረው በግለሰቦቹ ቁጥር ልክ የሆነ የተለያየ "እውነት" ነው። ይህ ሁኔታ ክርስትና ምንድን ነው? የሚለውን ነገር እንኳ መልክና ቅጥ የሌለው ያደርገዋል። በኦርቶዶክሳዊው የክርስትና አስተምህሮና በኑፋቄ መካከል ያለውን ድንበር ያጠፋዋል። ብሎም ሁሉንም ነገር አንጻራዊና ግለሰባዊ በማድረግ የመጽሐፍ ቅዱስን እውነተኛ ትምህርት በማደብዘዝና የእውነትንና የሐሰትን ድንበር በማጥፋት ሐሰት እንዲነግሥና ለዘብተኝነት እንዲለመድ፣ ስለ እውነት መናገርና ጥብቅና መቆም እንዲዳከምና ብሎም እንዲከስም ያደርጋል።

ስለዚህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ አንተን ራስህን ከቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ በላይ፣ ከቀደሙ ሰማዕታትና ቅዱሳን አባቶች አረዳድና አስተምህሮ በላይ ስለሚያስቀምጥህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ማለት "እኔ ብቻ" ማለት ነው። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው የተጀመረው የተሐድሶ ፕሮቴስታንት እንቅስቃሴ ዛሬ በምዕራቡ ዓለም የደረሰው ከዚህ ፍጻሜ ላይ ነው።

## 2. ለመረዳት ቀላል አለመሆኑን ይናገራል።

መጽሐፍ ቅዱስ እርሱ ራሱ ስለ ራሱ ከሚናገራቸው ነገሮች አንዱ ሲነበብ ጥንቃቄ እንደሚያስፈልገውና የሚያነበው ሁሉ መልእክቱን ሳይሳሳት የመረዳት ዋስትና የሌለው መሆኑን ነው። ይህን በተመለከተ ሐዋርያው ቅዱስ ጴጥሮስ በመልእክቱ ላይ በሚገባ ያልተማሩ ሰዎች የቅዱስ ጳውሎስን መልእክቶች በራሳቸው ስሜትና አረዳድ እየተረጎሙ ለሕይወት የተጻፉትን ትምህርቶች ለጥፋታቸው እንዳጣመሟቸው በመናገር ከዚህ ዓይነት ስህተት እንዳንወድቅ በጽኑ ያስጠነቅቃል፤ እንዲህ በማለት፦

> እንዲህም የተወደደው ወንድማችን ጳውሎስ ደግሞ እንደ ተሰጠው ጥበብ መጠን ጻፈላችሁ፤ በመልእክቱም ሁሉ ደግሞ እንደ ነገረ ስለዚህ ነገር ተናገረ። **በእነዚያ ዘንድ ለማስተዋል የሚያስቸግር ነገር አለ፤** ያልተማሩትና የማይጸኑትም ሰዎች **ሌሎችን መጻሕፍት እንደሚያጣምሙ እነዚህን ደግሞ**

ለገዛ ጥፋታቸው ያጣምማሉ። እንግዲህ እናንተ፣ ወዳጆች ሆይ፣ ይህን አስቀድማችሁ ስለምታውቁ፣ በዓመፀኞቹ ስሕተት ተስባችሁ ከራሳችሁ ጽናት እንዳትወድቁ ተጠንቀቁ። 2 ጴጥ. 3፡15-17

በዚህ ጥቅስ ላይ፣ የመጽሐፍ ቅዱስን አረዳድ በተመለከተ አራት መሠረታዊ ነገሮችን መገንዘብ እንችላለን። እነዚህም፡-

ሀ) የመጽሐፍ ቅዱስን ትክክለኛውን ሐሳቡን ለማወቅ መማር የሚያስፈልግ መሆኑን፣ በትክክለኛው መንገድ አለመማር ደግሞ ለተሳሳተ አረዳድ (ለማጣመም) የሚያጋልጥ መሆኑን፤ "ያልተማሩትና የማይጸኑትም ሰዎች ሌሎችን መጻሕፍት እንደሚያጣምሙ እነዚህን ደግሞ ለገዛ ጥፋታቸው ያጣምማሉ" ያለው ለዚህ ነውና። ባዶ ዕቃ ቀድሞ የሚቀመጥበትን ነገር መያዙ አይቀርምና።

ለ) የመጽሐፍ ቅዱስን ትርጉም ለማጣመም የሚቻል ነገር ብቻ ሳይሆን ይህ የመጻሕፍትን ቃል ማጣመም ያን ጊዜውኑም ገና ከጥንቱ የቤተ ክርስቲያን ዘመን አንሥቶ፣ መጻሕፍቱን የጻፏቸው ቅዱሳን ሐዋርያት በሕይወተ ሥጋ እያሉ እንኳ የሚያጣምሟቸው ሰዎች የነበሩ መሆናቸውን፤

ሐ) መጽሐፍ ቅዱስ በቀላሉ ሊረዷቸው የማይችሏቸው ወይም ለሁሉም ሰው ግልጽ ያልሆኑ ሐሳቦች ያሉት መሆኑን፤ እና

መ) የመጽሐፍ ቅዱስን ቃል ትርጉሙን ማጣመም ራስን ወደ ማጥፋት የሚወስድ የጥፋት መንገድ መሆኑን ነው። "ለገዛ ጥፋታቸው ያጣምማሉ" ብሏልና።

ጌታችን በመዋዕለ ሥጋዌው በሚያስተምርበት ወቅት ሰዱቃውያን የተባሉት የአይሁድ ቡድኖች ወደ እርሱ ቀርበው እንዲህ የሚል ጥያቄ እንዳቀረቡለት በቅዱስ ወንጌል ላይ ተጽፏል፡-

> በዚያን ቀን፣ ትንሣኤ ሙታን የለም የሚሉ ሰዱቃውያን ወደ እርሱ ቀረቡ፣ እንዲህም ብለው ጠየቁት፡- መምህር ሆይ፣ ሙሴ አንድ ሰው ልጅ ሳይወልድ ሲሞት ወንድሙ ሚስቱን አግብቶ ለወንድሙ ዘር ይተካ አለ። ሰባት ወንድማማች በእኛ ዘንድ ነበሩ፤ ፊተኛውም ሚስት አግብቶ ሞተ፣ ዘርም ስለሌለው ሚስቱን ለወንድሙ ተወለት፤ እንዲሁ ደግሞ ሁለተኛው ሦስተኛውም፣ እስከ ሰባተኛው ድረስ። ከሁሉም በኋላ ሴቲቱ ሞተች። ሁሉ አግብተዋታልና በትንሣኤ ቀን ከሰባቱ ለማናቸው ሚስት ትሆናለች?

ይህን ጥያቄያቸውን ካዳመጠ በኋላ መድኃኒታችን ደግሞ እንዲህ ብሎ መለሰላቸው፡-

> ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አላቸው፡- መጻሕፍትንና የእግዚአብሔርን ኃይል አታውቁምና ትስታላችሁ። በትንሣኤስ እንደ እግዚአብሔር መላእክት በሰማይ ይሆናሉ እንጂ አያገቡም አይጋቡምም። ስለ ትንሣኤ ሙታን ግን፤ እኔ የአብርሃም አምላክ የይስሐቅም አምላክ የያዕቆብም አምላክ ነኝ የሚል ከእግዚአብሔር ዘንድ ወደ እናንተ የተባለውን አላነበባችሁምን? የሕያዋን አምላክ ነው እንጂ የሙታን አይደለም። ሕዝቡም ይህን ሰምተው በትምህርቱ ተገረሙ። ማቴ. 22:23-33

የሰዱቃውያን ስህተት የተፈጠረው በኦሪቱ የተጻፈውን ትእዛዝ በአግባቡ ካለመረዳት እንጂ ካለማንበብ አልነበረም። ጌታችን "መጻሕፍትንና የእግዚአብሔርን ኃይል አታውቁምና ትስታላችሁ" ያላቸው ለዚህ ነበር። ስህተታቸው ያ ቃል ስለ መጻፉ አለማወቅ ሳይሆን ያን የሚያውቁትን ቃል ትርጉሙን በትክክል ያለመረዳት ችግር ነበር። ስለዚህም ጌታችን ቃሉን አብራርቶ ተርጉሞ ነገራቸው። "ሕዝቡም ይህን ሰምተው በትምህርቱ ተገረሙ" የተባለውም ገጸ ንባቡን ሰምተው አያውቁ ስለነበር ሳይሆን ያን ንባቡን እየሰሙት የኖሩትን ቃል ከሰዱቃውያን የተሳሳተ አረዳድ በተለየ መልኩ በእውነተኛው መንገድ ተርጉሞ ስላስተማራቸው ነበር። በዚህ የጌታችን ትርጉም የተደሰቱትም ሕዝቡ ብቻ ሳይሆኑ ከሰዱቃውያን ጋር የእምነትም የጥቅምም ግጭት የነበራቸው ፈሪሳውያን የተባሉት ሊላኛዎቹ የአይሁድ ቡድኖችም ነበሩ። ፈሪሳውያን የተደሰቱበት ምክንያት ደግሞ እውነትን በመስማታቸው ሳይሆን ተቀናቃኞቻቸው የነበሩትን ሰዱቃውያንን ስላሳፈረላቸውና ዝም ስላሰኘላቸው ነበር፤ "ፈሪሳውያንም ሰዱቃውያንን ዝም እንዳሰኛቸው በሰሙ ጊዜ አብረው ተሰበሰቡ" እንዲል። ማቴ. 22:34

ከዚያው ቀጥሎ መድኃኒታችን ፈሪሳውያን ወደ እርሱ ተሰብስበው ስለቀረቡ የሚጠቅማቸውን ትምህርት ያገኙ ዘንድ የመሢሑን (የእርሱን) ማንነት በተመለከተ በጣም መሠረታዊ የሆነ ጥያቄ ጠየቃቸው። ጥያቄው እና ምልልሱ እንዲህ የሚል ነበር፡-

> ፈሪሳውያንም ተሰብስበው ሳሉ፤ ኢየሱስ፡- ስለ ክርስቶስ ምን ይመስላችኋል? የማንስ ልጅ ነው? ብሎ ጠየቃቸው። እነርሱም የዳዊት ልጅ ነው አሉት። እርሱም፡- እንኪያስ ዳዊት፤ ጌታ ጌታዬን፤ ጠላቶችህን የእግርህ መረገጫ እስካደርግልህ ድረስ በቀኜ ተቀመጥ አለው ሲል እንዴት በመንፈስ ጌታ ብሎ ይጠራዋል? ዳዊትስ ጌታ ብሎ ከጠራው፤ እንዴት ልጁ ይሆናል? አላቸው። አንድም ቃል ስንኳ ይመልስለት ዘንድ የተቻለው የለም፤ ከዚያ ቀንም ጀምሮ ወደ ፊት ማንም ሊጠይቀው አልደፈረም። ማቴ. 22:41-46

ፈሪሳውያን በጌታችን የተጠየቁት ጥያቄ ሁል ጊዜ በየቀኑ ከሚጸልዩትና ከሚያነቡት ከዳዊት መዝሙር ላይ ያለ ቃል ነው። ለእግዚአብሔር ሕግ ቀናተኞች ነን፣ ሕጉን እንጠነቅቃለን ባዮች የሆኑት ፈሪሳውያን እንገታቸውን እያወዛወዙ "ጌታ ጌታዬን፣ ጠላቶችህን የእግርህ መረገጫ እስካደርግልህ ድረስ በቀኜ ተቀመጥ አለው" የሚለውን ቃለ ዳዊት በየጊዜው በቃላቸው ያነበንቡታል። ሆኖም ይህ በቃላቸው የሚናገሩት ቃል ምን ማለት እንደሆነ ሲጠየቁ ግን "አንድም ቃል ስንኳ ይመልስለት ዘንድ የተቻለው የለም።" ለምን የመጽሐፍ ቅዱስን ቃል ማንበብ ማለት ያን ቃል ሐሳቡን በትክክል ማወቅና መረዳት ማለት አይደለምና። እንደዚያማ ቢሆን ኖሮ ቃለ ንባቡን ደጋና አድርገው የሚያውቁትንና በየቀኑ የሚያነብቡትን ቃል ሲጠየቁ ሰተት አድርገው መልስ መስጠት በቻሉ ነበር።

እንግዲህ እስካሁን ያየናቸው የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶች ሁሉም በአንድ ቃል ተባብረው የሚናገሩት "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ ከመጽሐፍ ቅዱስ ጋር በቀጥታ የሚቃረን የስህተት ትምህርት መሆኑን ነው። መጽሐፍ ቅዱስ በግልጽና በማያሻማ ቃል ደጋግሞ የሚናገረው መጽሐፍ ቅዱስን በማንበብ ብቻ ማንም ሰው በትክክል ሐሳቡን መረዳት ይችላል፤ እርሱ በገባው መንገድም መተርጎም ይችላል የሚል ሳይሆን ከዚህ በተቃራኒ ማንበብ ማለት መረዳት አለመሆኑን፣ ማንም ሰው መጽሐፍ ቅዱስን በግሉ አረዳድ መተርጎም እንደሌለበት፤ ቅዱሳት መጻሕፍትን በተሳሳተ መንገድ የሚያጣምሙ ሰዎች መኖራቸውንና በእነርሱ ስህተት ተጠልፎ ላለመውደቅ ጥንቃቄ ማድረግ የሚገባ መሆኑን ነው።

ታዲያ መጽሐፍ ቅዱስን በትክክል ለመረዳት ምን እናድርግ? ለዚህ መፍትሔው መጽሐፍ ቅዱስን ከጻፈችው፣ ብዙና ለመለየት ቀላል ካልነበሩ የመናፍቃን የማሳሳቻ መጻሕፍት መካከል ለይታ በመረጠችውና አንድ አድርጋ በቀኖና በሰበሰበችው፣ ሐዋርያዊትና ኦርቶዶክሳዊት በሆነችው በቅድስት ቤተ ክርስቲያን አረዳድ መንፈስ መረዳት ነው። ይህም ቤተ ክርስቲያናዊ አረዳድ የሚባለው ነው።

### 1.10.2 ቤተ ክርስቲያናዊ የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድ

መጽሐፍ ቅዱስን የሚያነብብ ሰው በመጽሐፉ ውስጥ ያለውን የእግዚአብሔር መልእክት በትክክል ለመረዳትና ወደ ሕይወት ለመድረስ፣ ከስህተትም ለመጠበቅና ሕይወት በሆነው ቃሉ ላለመሰናከል ማድረግ የሚገባው ነገር አለ። ይህም የግሉን አረዳድ ከመከተል ይልቅ መጽሐፍ ቅዱስን ከመጀመሪያው ጀምሮ በውስጧ የያዘችውና የአስተምህሮዋ ዋና አካል ያደረገችው ቅድስት ቤተ ክርስቲያን

የመጽሐፉን ቃል ከሐዋርያት ጀምሮ እንዴት እንደ ተረዳችውና እንዴት በሕይወት ስትተገብረው እንደ ኖረች መረዳት ነው። ይህ መጽሐፍ ቅዱስን በትክክል መረዳት ለሚፈልግ ሰው ሁሉ አማራጭ የሌለው ነገር ነው። መጽሐፍ ቅዱስን በማንበብ ብቻ ወደ አንድ ዓይነት አረዳድና እምነት መድረስ የማይቻል መሆኑን የራሳቸው የፕሮቴስታንቶች እሳቤኝ መከፋፈልና መለያየት ተግባራዊ ምስክርና ማስረጃ መሆኑን ከላይ አይተናል። ከእነርሱ በፊት የነበሩት የተለያዩ መናፍቃንም የሐዋርያዊት ቤተ ክርስቲያን ገንዘብ ከሆነው መጽሐፍ ቅዱስ እየጠቀሱ የሚያስተምሩት ትምህርት ግን የተሳሳተ ነበር። ስህተቱ የተፈጠረውም ከአረዳዳቸውና ከአተረጓጎማቸው እንጂ ከመጽሐፉ ቃል (ከገጸ ንባቡ) አልነበረም።

መጽሐፍ ቅዱስን ለሚያነብ ሰው ቤተ ክርስቲያናዊ የሆነ የአረዳድ መንፈስ ለምን አስፈላጊ እንደሆነ በ5ኛው መቶ ዓመት ላይ የነበረው አባት የሌሪንሱ ቪንሴንት (Vincent of Lérins) እንዲህ ብሎ አብራርቶ ጽፏል፡-

> "መናፍቃንም ከመጽሐፍ ቅዱስ ይጠቅሳሉ እንዴ?" ብሎ የሚጠይቅ ሰው ይኖር ይሆናል። አዎ፣ ይጠቅሳሉ እንጂ፣ እንዲያውም አብዝተውና አትረፍርፈው ይጠቅሳሉ። ከእያንዳንዱ የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍል ውስጥ ይጠቅሳሉ። ከሙሴ መጻሕፍት፣ ከመጽሐፈ ነገሥት፣ ከመዝሙራት፣ ከነቢያት፣ ከወንጌላት፣ ከመልእክታት ሁሉ ይጠቅሳሉ። በግላቸውም ሆነ በቡድን፣ ሲናገሩም ሆነ ሲጽፉ፣ በጎዳና ላይም ሆነ በስብሰባዎቻቸው፣ ከመጽሐፍ ቅዱስ በሚጠቅሷቸው ጥቅሶች ሳይሸፍኑ የሚያደርጉት አንድም ነገር የለም። የጳውሎስ ሳምሳጣን፣ የአርዮስን፣ የዩኖሚየስን፣ የጆቪኒያንን፣ የንስጥሮስን፣ የሌሎችንም መናፍቃን ድርሰቶች በሙሉ ተመልከት። በእነዚህ መናፍቃን በሁሉም ጽሑፎቻቸው ውስጥ ስፍር ቁጥር የሌላቸው የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶችን ተደርድረው ታገኛለህ። ከብሉይ ኪዳንም ሆነ ከሐዲስ ኪዳን በተወሰዱ ጥቅሶች እውነተኛ የመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት እንዲመስል ተደርጎ ያልቀረበ አንድም ገጽ አታገኝም።

ሆኖም ራሳቸውን በአምላካዊው ቃል በደበቁ መጠን የበለጠ ሊፈሩና ጥንቃቄ ሊደረግባቸው ይገባል። የአስተምህሯቸው ክፉ ሽታ ያለውን መጥፎ ጠረን መልካም አስመስለው ለማቅረብ የሚያስችላቸውን ዘዴ ሳይጠቀሙ እንዲሁ እንዳለ በግልጽ ከተተነፈሰ ተቀባይነት ለማግኘት እጅግ አስቸጋሪ እንደሚሆንባቸው ያውቃሉና። ይህም የሰዎችን ኑፋቄ ለመቃወምና ለማውገዝ ፈጣንና ዝግጁ የሆነው ሰው፣ አምላካዊ ቃሎችን ለማውገዝ ግን እንዲያመነታ ለማድረግ በላዩ ላይ የመጽሐፍ ቅዱስን ሽቱ ያርከፈከፉበታል። ነርሶች ወይም

እናቶች ለሕፃናት መራራ መድኃኒት ሊሰጡ ሲሉ የመድኃኒቱን መስጫ ጫፍ በማር ወይም በሌላ ጣፋጭ ነገር እንደሚቀቡትና ይህን ያላወቀው ሕፃንም መጀመሪያ በሚቀምሰው በጣፋጩ ነገር ተታልሎ መራራውን ነገር መልካም መስሎት እንደሚወስደው ዓይነት ማለት ነው።

መድኃኒታችን "የበግ ለምድ ለብሰው ከሚመጡባችሁ በውሥጣቸው ግን ነጣቂዎች ተኩላዎች ከሆኑ ከሐሰተኞች ነቢያት ተጠንቀቁ" ያለው ለዚህ ነው። ማቴ. 7፥15 "የበግ ለምድ" ማለት ምን ማለት ነው? "በግ" የተባለው "የዓለምን ኃጢአት የሚያስወግድ" የተባለው ጌታችንን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሲሆን፣ "ለምዱ" ደግሞ የእርሱ ቃል ነው። ነጣቂዎች ተኩላዎች የተባሉትስ? ነጣቂዎች ተኩላዎች የተባሉት የበጉን የክርስቶስን ቃል ለብሰው የእርሱ በጎች የሆኑትን ምእመናንን በአምላካዊው ቃል እየነጠቁ የሚወስዱቸውና የሚገድሏቸው መናፍቃን ናቸው። እነርሱ በበግ ለምድ ውስጥ የተደበቁ ተኩላዎች መሆናቸውን ያላወቋቸውንና የማይጠረጥሯቸውን ምእመናንን አብዝተው ለመንጠቅና ለመግደል ያመቻቸው ዘንድ ራሳቸውን በመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ውስጥ ይደብቃሉ። በጎቹም የተኩላው ውጫዊ ገጽ በግ ስለ መሰለ ከበጎች ጋር ያሉ እየመሰላቸው ከውስጣቸው ገብተው በሚፈጇቸው ተኩላዎች ይበላሉ።

ጌታችን ምን አለ? "ከፍሬያቸው ታውቋቸዋላችሁ" አለ። ይህም ማለት እነዚያን አምላካዊ ቃላት ሲጠቅሷቸው ብቻ ሳይሆን ሲተረጉሟቸውና እናብራራቸዋለን ሲሉ፣ የእነርሱን ኑፋቄ የሚደግፉና የሚያስተምሩ አስመስለው አጣምመው ሊተረጉሟቸው ሲሉ፣ ያን ጊዜ መራራነታቸው፣ የስህተት ትምህርታቸውና ማንነታቸው ይገለጣል። በመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ ከድነውት የነበረው የክህደታቸው መጥፎ ሽታ ያን ጊዜ ወደ ውጭ ይወጣና ክርፋቱ መሽተት ይጀምራል። ያን ጊዜ የፈጠራ ትምህርቶቻቸው ይገለጡባቸዋል። ያን ጊዜ የአባቶችን ድንበሮች ማፍረሳቸው፣ ሐዋርያዊውን አረዳድና እምነት መቃወማቸው፣ የቤተ ክርስቲያንን አስተምህሮ ማፍረሳቸው ገሃድ ይወጣባቸዋል። ያን ጊዜ የማስመሰል ለምዳቸው ይቀደድና እውነተኛ ማንነታቸው ይታያል። ስለዚህ እውነተኛውንና የበግ ለምድ የለበሰውን ተኩላ ለይቶ ማወቅ የሚቻለው "ከፍሬያቸው" - ማለትም ከአተረጓጎማቸው ነው ማለት ነው።

ሐዋርያው ቅዱስ ጳውሎስ በሁለተኛው የቆሮንቶስ መልእክቱ ላይ "እንደ እነዚህ ያሉ ሰዎች የክርስቶስን ሐዋርያት እንዲመስሉ ራሳቸውን እየለወጡ፣ ውሸተኞች ሐዋርያትና ተንኮለኞች ሠራተኞች ናቸውና" በማለት የገለጻቸው እንደ እነዚህ ያሉትን ነው።

2 ቆሮ. 11፡13 ሐዋርያት ከመጽሐፍ ቅዱስ ይጠቅሱ ነበር፣ እነዚህ ሰዎችም እንዲሁ ይጠቅሱ ነበር። ሐዋርያት ከመዝሙራት ይጠቅሱ ነበር፤ እነዚህም እንዲሁ ይጠቅሱ ነበር። ሐዋርያት ከነቢያት ይጠቅሱ ነበር፤ እነዚህም ይጠቅሱ ነበር። ሆኖም በመጥቀስ ደረጃ ሁለቱም ከተስማሙባቸው መጻሕፍት የጠቀሷቸውን ጥቅሶች በተለየ መንገድ ሲተረጉሟቸው፣ ያን ጊዜ ትክክለኛው አተረጓጎምና አረዳድ ከስህተቱ፣ እውነተኛው ከሐሰቱ፣ ቀጥተኛው ከጠማማው ተለይቶ ታወቀ፤ በአንድ ቃልም እውነተኞቹ ሐዋርያት ከአስመሳዮቹ ተለይተው ታወቁ። ሐዋርያው እንዳለው "ይህም ድንቅ አይደለም፤ ሰይጣን ራሱ የብርሃንን መልአክ እንዲመስል ራሱን ይለውጣልና፤ እንግዲህ አገልጋዮቹ ደግሞ የጽድቅን አገልጋዮች እንዲመስሉ ራሳቸውን ቢለውጡ ታላቅ ነገር አይደለም።" 2 ቆሮ. 11፡14-15

እንግዲህ ቅዱስ ጳውሎስ እንዳስተማረን ሐሰተኛ መምህራንም እንደ እውነተኞቹ መምህራን የራሳቸውን የፈጠራ ትምህርት የሚሸፍኑባቸውንና እውነት አስመስለው ለማቅረብ የሚጠቀሙባቸውን ጥቅሶች ከመጽሐፍ ቅዱስ ይጠቅሳሉ። ይህን ሲያደርጉም መጽሐፍ ቅዱስን የሚቀበልና የሚጠቅስ መስሎ ካልታየ በስተቀር ስህተትን አሹልኮ ለማስገባት በቀላሉ እንደማይችል ስለተረዳ አባታቸው ዲያብሎስ የቀየሰውን ስልት መከተላቸው ነው። ዲያብሎስ ጌታችንን እንኳ የፈተነው ከመጽሐፍ ጠቅሶ "መላእክቱን ስለ አንተ ያዝልሃል፣ እግርህንም በድንጋይ ከቶ እንዳትሰናከል በእጃቸው ያነሡሃል ተብሎ ተጽፏልና የእግዚአብሔር ልጅስ ከሆንህ፣ ወደ ታች ራስህን ወርውር አለው" ተብሎ እንደ ተጻፈ ብሎ ጥቅስ ጠቅሶ ነውና። ማቴ. 4፡5-7

ዲያብሎስ ጌታችንን "ተብሎ ተጽፏልና" ብሎ እንደ ፈተነው፣ ዛሬም ማንም ሰው የሆነ ጥቅስ ጠቅሶ "መጽሐፍ ቅዱስ እንዲህ ይላል" ቢለን ጥንቃቄ ልናደርግ ያስፈልጋል። **ሰዎች ከሐዋርያት ወይም ከነቢያት ጥቅሶችን ይዘው ከሐዋርያዊት ቤተ ክርስቲያን እምነትና አስተምህሮ ተቃራኒ የሆነ ነገር ካመጡ በእነርሱ ውስጥ እየተናገረ ያለው ዲያብሎስ መሆኑን መረዳት አለብን።** የእነርሱ ራስ ዲያብሎስ የእኛን ራስ ጌታን በጥቅስ እንደ ፈተነው፣ አሁን ደግሞ የእርሱ ጭፍሮችና አካላት የሆኑት መናፍቃን የክርስቶስ አካላት የሆንን እኛን ይፈትኑናል። መናፍቃን ከመጽሐፍ ቅዱስ መጥቀሳቸው ራሳቸው የሆነውን የዲያብሎስን አርአያ በመከተል ነው። የእኛ ራስ ጌታ በአጋንንት ራስ በጥቅስ እንደ ተፈተነ የእርሱ አካላት የሆንን እኛ ደግሞ የዲያብሎስ ጭፍራዎች በሆኑት በመናፍቃን በጥቅስ እንፈተናለን። ዲያብሎስ ጌታን "ከመቅደስ ወደ ታች ራስህን ወርውር" ብሎ በጥቅስ እንደ ፈተነው

> መናፍቃንም ራሳችንን መቅደስ ከሆነች አንዲት ቤተ ክርስቲያን ወደ ኑፋቄና ክህደት እንወረውር ዘንድ በጥቅስ ይፈትኑናል።[86]

ነገሩ እንዲህ ከሆነ፣ መጽሐፍ ቅዱስን በትክክል ለመረዳት ምን እናድርግ? ለዚህ መፍትሔው ምን እንደሆነ ይኸው አባት ይቀጥልና እንዲህ ይመክራል፡-

> ሐዋርያዊት በሆነችው ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ጤናማ ሆኖ ለመኖርና እስከ መጨረሻው ለመጽናት፣ እንዲሁም የመናፍቃንን አስመሳይ የሆኑ ማታለያዎችን ለይቶ ለማወቅና ከወጥመዶቻቸው ለመዳን እንችል ዘንድ እምነታችንን በሁለት (2) መንገዶች መጠበቅ አለብን፤ እነዚህም፡-
>
> 1ኛ) አምላካውያት በሆኑት በቅዱሳት መጻሕፍት ትምህርት ሲሆን
>
> 2ኛ) ደግሞ በኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን የመጽሐፍ ቅዱስ አተረጓጎምና አረዳድ መንፈስ (በትውፊት) ነው።
>
> ነገር ግን እዚህ ላይ መጽሐፍ ቅዱስ ስለ ሀሉም ነገር በቂና ከበቂ በላይ ስለሆነ ከእርሱ ጋር የቤተ ክርስቲያንን ትርጓሜና አረዳድ መደረቡ ለምን ያስፈልጋል? ብሎ የሚጠይቅ ሰው ይኖር ይሆናል። ይህ የሚያስፈልገው ስለዚህ ምክንያት ነው፡- መጽሐፍ ቅዱስ እጅግ ጥልቅ ከመሆኑ የተነሣ የሚያነቡት ሁሉም በአንድ ዓይነት መንፈስ አይረዱትም። ነገር ግን አንዱ እንደዚህ፣ ሌላው እንደዚያ ነው የሚረዱት። ከዚህም የተነሣ በተርጓሚው ቁጥር ልክ ሊተረጎም የሚችል ይመስላል። መርቅያን በአንድ በኩል ይተረጉመዋል፣ ሰባልዮስ ደግሞ በሌላ መልኩ ይተረጉመዋል፣ አርዮስ፣ ዩኖሚየስ፣ መቅዶንዮስ፣ ፎጢኖስ፣ አቡሊናርዮስ፣ ንስጥሮስ፣ . . . ሁሉም አተረጓጎማቸው የአንዱ ከሌላው የተለያየ ነው።
>
> እነዚህ ሁሉ መናፍቃን ትምህርታቸው ከመጽሐፍ ቅዱስ የተገኘ መሆኑን ለማሳየት ከብሉይ ኪዳን እስከ ሐዲስ ኪዳን ብዙ ጥቅሶችን ይደረድራሉ። 'እኛ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ሌላ ነገር አላመጣንም' ይላሉ። ሆኖም ግን የትምህርታቸው ይዘት ሲታይ ከመጽሐፍ ቅዱስ ሃሳብ ተቃራኒ ሆኖ እናገኘዋለን። የዚህ ምክንያቱ ደግሞ ጥሬ ቃሉን ከመጽሐፍ ቅዱስ ወሰዱ እንጂ ትርጓሜው የራሳቸው ስለሆነ ነው።
>
> የቅዱሳት መጻሕፍት ይዘትና ምሥጢር በጣም ጥልቅና ውስብስብ ስለሆነ እንደ እነዚህ መናፍቃን ከተሳሳተ የግል አተረጓጎምና ከባድ ስህተት ውስጥ

[86] The Commonitory of Vincent of Lérins: Ch. 25-28

> ላለመግባት የመጽሐፍ ቅዱስን ቃል የምንረዳበት መንገድ በቤተ ክርስቲያን የአረዳድና አተረጓጎም መንፈስና መንገድ መሆን አለበት። ቅዱሳን ሐዋርያት፣ ደማቸውን ያፈሰሱና ሰማዕት የሆኑ፣ ስለ ክርስቶስ የመሰከሩ፣ መከራ የተቀበሉ፣ በቅድስና የኖሩ አባቶቻችን ከተረዱበት አረዳድና አተረጓጎም እንዳንወጣ ከፍተኛ ጥንቃቄ ያስፈልገናል።[87]

ቤተ ክርስቲያናዊ ከሆነ አረዳድ ወጥቶ መጽሐፍ ቅዱስን የምረዳው በራሴ መንገድ ብቻ ነው፣ ትክክለኛው ትርጉም የእኔ ነው የሚል ካለ፣ እንደዚህ ያለውን ሰው ሐዋርያው ቅዱስ ጳውሎስ "ምን ነው? የእግዚአብሔር ቃል የወጣ ከእናንተ ነውን? ወይስ ወደ እናንተ ብቻ ደርሷልን?" ብሎ ይጠይቀዋል። 1 ቆሮ. 14:36

## መጽሐፍ ቅዱስ - በውስጡ ብዙ ሀብት እንዳለው ሰፊና ለም የእርሻ ማሳ

ቅዱስ ዮሐንስ ካስያን የተባለው በ4ኛው መቶ ዓመት ማብቂያና በ5ኛው መቶ ዓመት መጀመሪያ ላይ የነበረው አባት በግብፅ በረሃ ውስጥ የነበሩ ታላላቅ ገዳማውያን አባቶች በተለያዩ ጉዳዮች ላይ የሰጧቸውን ትምህርቶች "ጉባኤያት - Conferences" በሚል ርእስ ጽፎልናል። በዚህ መጽሐፉ ውስጥ ከጻፋቸው ትምህርቶች አንዱ መጽሐፍ ቅዱስን ሰው እንዴት ሊረዳው እንደሚገባ በተመለከተ ነው። በዚህ ላይ አባ ሴሬኔዎስ ከተባለው ገዳማዊ አባት የሰማውን ትምህርት እንደሚከተለው ጽፎልናል፡-

> መጽሐፍ ቅዱስ በውስጡ ብዙ ሀብት እንደያዘ ሰፊና ለም የእርሻ ማሳ ነው። በዚህ እርሻ ውስጥ ሦስት (3) ዓይነት ሰብሎች ይኖራሉ። እነዚህም (1) ማብሰል ሳያስፈልጋቸው እንዳሉ በጥሬያቸው ሊበሉ የሚችሉ፣ (2) ካልበሰሉ ሊበሉ የማይችሉ፣ ይልቁንም ሊጎዱ የሚችሉ፣ እና (3) በጥሬውም ሆነ በስለው ሊበሉ የሚችሉ (ሲበስሉ የበለጠ ቢጣፍጡም በጥሬያቸውም ቢበሉ የማይጎዱ) ናቸው። ከዚህ ውጭ ለእንስሳት መኖ የሚሆን ሳርና መሰል ነገርንም ያበቅላል። በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥም እንደዚሁ ሦስት ዓይነት ትርጓሜ ሳያስፈልጋቸው በጥሬያቸው ሊበሉ እንደሚችሉት ቃሎች አሉ። መልእክታቸው ግልጽ የሆነ ማንም ሰው በቀላሉ ሊረዳቸው የሚችላቸውና የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች አሉ። ካልበሰሉ ሊበሉ እንደማይችሉት ሰብሎች ካልተተረጎሙ ለመረዳት አስቸጋሪ የሆኑ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች አሉ።

[87] The Commonitory of Vincent of Lérins, Ch. 25-28.

በጥሬውም ሆነ በስለው ሊበሉ እንደሚችሉት የሰብል ዓይነቶች ደግሞ በጥሬ ቃሉም መረዳት የሚቻል፣ በትርጓሜም ሊብራሩ የሚችሉ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች አሉ።"[88]

እነዚህን ከዚህ ቀጥሎ እንመልከት።

**ሀ) ማንም ሰው በቀላሉ ሊረዳቸው የሚችላቸው የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች**

በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ መልእክታቸው ግልጽ የሆኑና ትርጓሜ የማያሻቸው ብዙ ቃሎች አሉ። ለምሳሌም፡-

- ✓ "እስራኤል ሆይ፣ ስማ፤ አምላካችን እግዚአብሔር አንድ እግዚአብሔር ነው።" ዘዳ. 6:4
- ✓ "አምላክህን እግዚአብሔርን በፍጹም ልብህ በፍጹምም ነፍስህ በፍጹምም ኃይልህ ውደድ።" ዘዳ. 6:4-5
- ✓ "ከእኔ በቀር ሌሎች አማልክት አይሁኑልህ።" ዘጸ. 20:3

**ለ) በምሥጢር ውስጥ የተሰወሩና እነርሱን ለመረዳት ብዙ ጥበብና ጥንቃቄ የሚያስፈልጋቸው የመጽሐፍ ቅዱስ ቃሎች**

ለምሳሌም፡-

- ✓ "አሁን ግን ኮረጆ ያለው ከእርሱ ጋር ይውሰድ፣ ከረጢትም ያለው እንዲሁ፤ የሌለውም ልብሱን ሸጦ ሰይፍ ይግዛ።" ሉቃ. 22:36
- ✓ "በምድር ላይ እሳት ልጥል መጣሁ፣ አሁንም የነደደ ከሆነ ዘንድ ምን እፈልጋለሁ?" ሉቃ. 12:49
- ✓ "ነገር ግን እነዚያን በላያቸው ልነግሥ ያልወደዱትን ጠላቶቼን ወደዚህ አምጧቸው፣ በፊቴም እረዷቸው።" ሉቃ. 19:27
- ✓ "ስለዚያች ቀንና ስለዚያች ሰዓት ግን ከአባት ብቻ በቀር የሰማይ መላእክትም ቢሆኑ ልጅም ቢሆን የሚያውቅ የለም።" ማቴ. 24:36
- ✓ "ከእኔ አብ ይበልጣል" ዮሐ. 14:28

ሳይበስሉ በጥሬያቸው ቢበሉ እንደሚያምሙ እህሎች እነዚህ የመጽሐፍ ቅዱስ ምንባቦችም በጥሬያቸው (በገጸ ንባባቸው) ብቻ ይወሰዱ ከተባለ ከስህተት ላይ መውደቅንና በሃይማኖት ጤናማ አለመሆንን ሊያስከትሉ ይችላሉ። ያነበባቸው ሁሉ በቀላሉ ሊረዳቸው አይችልምና።

[88] St. John Cassian, *Conferences*, Chapter 3, Conf

እግዚአብሔር እንደዚህ ያደረገባቸው ብዙ ምክንያቶች አሉ። ጌታችን በመዋዕለ ሥጋዌው ለተለያዩ ሰዎች ሲያስተምርበት ካየነው ሁኔታ በሰዎች ዘንድ የተለያዩ የመረዳት ደረጃዎች እንዳሉ አሳይቶናል። ተአምራቱን ለማየትና የሚያበረክተውን ኅብስት ለመብላት ወደ እርሱ ይመጡ የነበሩትን የሰጣቸው "በመንገድ ዝለው እንዳይወድቁ ወደ ቤታቸው መድረሻ የሚበቃቸውን ያህል" ነበር። ለእነዚህ ዓይነት ሰዎች ብዙውን ነገር የነገራቸው በምሳሌ ነበር።

ከእግሩ ሥር ቁጭ ብለው ቃሉን በፍቅር ይሰሙት ለነበሩት ደግሞ (እንደ ማርያም እኅተ አልዓዛር ዓይነት - ሉቃ. 10:38-42) በዚያው መጠን ከፍ ያለ አረዳድንና ምስጢርን ይገልጥላቸው ነበር። ከዋለበት ለሚውሉትና ካደረበት ለሚያድሩት ለሐዋርያት ደግሞ ምሳሌውን እየተረጎመ የረቀቀውን እያብራራ ያስተምራቸው ነበር። ከሐዋርያትም ከእርሱ ጋር ወደ ደብረ ታቦር ለወጡት ለጴጥሮስ ለዮሐንስና ለያዕቆብ ደግሞ እግዚአብሔር አብ በደመና ሆኖ ሲናገር ድምፁን እንዲሰሙ፣ የሚያስደንቅ ብርሃን ሲገለጥ እንዲያዩና መንፈስ ቅዱስ ሲጋርዳቸው እንዲመለከቱ አስችሏቸዋል። ቅዱስ ጴጥሮስ በመልእክቱ ላይ "እኛም በቅዱሱ ተራራ ከእርሱ ጋር ሳለን ይህን ድምፅ ከሰማይ ሲወርድ ሰማን" እንዳለ። 2 ጴጥ. 1:18

ስለዚህ እግዚአብሔር ቃሉንና የቃሉን ምስጢር መረዳትን የሚሰጠው እንደ ሰዎቹ አቀራረብና ሁኔታ ነው ማለት ነው። ስለዚህ ሁሉም ሰው እኩል ጸጋ እንደማይኖረው ሁሉ እኩል የሆነ የእግዚአብሔርን ቃል የመረዳት ችሎታና ዓቅም አይኖረውም።

### ሐ) ግልጽም ጥልቅም መልእክት ያላቸው

ለምሳሌም፡-

- ✓ "በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሰማይንና ምድርን ፈጠረ።" ዘፍ. 1:1
- ✓ "ወንድሞች ሆይ፣ ይህን ታውቁ ዘንድ እወዳለሁ። አባቶቻችን ሁሉ ከደመና በታች ነበሩ ሁሉም በባሕር መካከል ተሻገሩ፤ ሁሉም ሙሴን ይተባበሩ ዘንድ በደመናና በባሕር ተጠመቁ፤ ሁሉም ያን መንፈሳዊ መብል በሉ፣ ሁሉም ያን መንፈሳዊ መጠጥ ጠጡ፤ ይከተላቸው ከነበረው ከመንፈሳዊ ዓለት ጠጥተዋልና፣ ያም ዓለት ክርስቶስ ነበረ።" 1 ቆሮ. 10:1-4

### መ) ለከብቶች መኖ የሚሆኑ -

አባ ሴሬኔዎስ በዚህ ጉዳይ ላይ የሰጠውን ትምህርቱን ሲያጠቃልል ይህ ዓይነት እርሻ አራተኛ ደግሞ ለእንስሳት መኖ የሚሆን ነገርን እንደሚያበቅል ሁሉ መጽሐፍ ቅዱስም "ሰብአ ወእንስሳ ታድኅን እግዚኦ - አቤቱ ሰውንና እንስሳን ታድናለህ" (መዝ.

35:6) እንደሚለው፣ እንደዚሁ አረዳዳቸው ዝቅ ያለ ለሆኑ ሰዎች የሚሆን "መኖ" አለው ይላል። እነዚህም እንደ ምሳሌዎች፣ ተረኮች፣ በእንስሳት ምሳሌነት የተገለጹ ትምህርቶችና ይህን የመሰሉት ናቸው ይላል። እነዚህ ረቀቅና ጠለቅ ያለውን የቅዱሳት መጻሕፍት ነገር ለመረዳት ለማይችሉ የሚሆኑ ቀላልና ግልጽ የሆኑ የታሪክ ትረካዎች ዓይነት ሲሆኑ ለዚህ ሊሆኑ የሚችሉ ነገሮች በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ብዙ አሉ።

### 1.10.3 በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ተነሥቶ የነበረው የአረዳድ (የአተረጓጎም) ጉዳይ (The hermeneutical question)

ከዘመነ ሐዋርያት ቀጥሎ የነበረው ዘመን ግኖስቲኮች የራሳቸውን የፈጠራ ትምህርት ለማስፋፋት ሰፊ ዘመቻ እያደረጉ የነበሩበት ዘመን ነበር። ግኖስቲኮች ከሐዋርያት በምስጢር የተቀበልነው ረቂቅ ትምህርት አለን እያሉ የራሳቸውን የፈጠራ ትምህርት ያሰራጩ ነበር። አንድ ማሳያ ብናነሣ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ብቸኛ አዳኝና መካከለኛ ሳይሆን ከአምላክ ወደ እኛ ከሚመጡት መልእክተኞች (ኤዎኖች) ሠላሳኛው ነው ይሉ ነበር። ይህን ልብ ወለድ ከየት አመጣችሁት? ሲባሉ፣ ጌታ በሠላሳ ዓመቱ የተጠመቀው ሠላሳኛው ኤዎን ስለሆነ ነው ብለው የጌታችንን በሠላሳ ዓመቱ መጠመቅ ለፈጠራ ትምህርታቸው ማስረጃ አድርገው ለመተርጎም ይሞክሩ ነበር። ይህም ኢየሱስ 30ኛው ኤዎን ለመሆኑ እኛ በምስጢር የተቀበልነው ትምህርት ነው እያሉ ወንጌልን ለራሳቸው የፈጠራ ትምህርት ማስረጃ እያደረጉ እያጣመሙ ይተረጉሙና ያስተምሩ ነበር።

በዚያን ዘመን ከነበሩት አባቶች አንዱ የነበረው ቅዱስ ሄሬኔዎስ፣ የእነዚያን መናፍቃን ትምህርት ስህተትነት የሚያጋልጥና ቤተ ክርስቲያን ከክርስቶስ በሐዋርያት እና በሐዋርያት ወራሾች አማካይነት የተቀበለችውን እውነተኛውን ትምህርት የሚያስረዳ **"በእንተ መናፍቃን** - Adversus Heresaes" የተሰኘ ግሩም መጽሐፍ ጽፏል። በዘመኑ የነበሩት መናፍቃን ግኖስቲኮች ቅዱሳት መጻሕፍትን እየጠቀሱ፣ ግን ከቤተ ክርስቲያን ውጭ የሆነ ባእድ ትምህርት እያስተማሩ ብዙዎችን ግራ ሲያጋቡ የተመለከተው ይህ አባት፣ በዚህ መጽሐፉ ላይ አንድ ምሳሌ መስሏል። ምሳሌውም እንዲህ የሚል ነው፡-

> ጠቢብ የሆነ አንድ ሠዓሊ ከብዙ የከበሩ ማዕድናት የተሠራ ውብ የሆነ የንጉሥ ምስል በሞዛይክ ሠራ። የሞዛይክ ሥዕል እውቀት የሌለው አንድ ሌላ ሰው ግን ያን የሞዛይክ ምስል ወስዶ ነጣጠለውና የከበሩትን ድንጋዮች መልሶ በሌላ መንገድ ገጣጠማቸው። ሆኖም ሞዛይኩ የንጉሡን መልክ

ሳይሆን የውሻ ወይም የቀበሮ መልክ እንዲመስል አድርጎ ገጣጠመው። ያን ጊዜ ሰውየው፣ በምስሉ ያሉት የከበሩ ድንጋዮች እነዚያው ራሳቸውና እውነተኛ የከበሩ ማዕድናት በመሆናቸው ምክንያት ብቻ "በመጀመሪያው ሠዓሊ የተሠራው የመጀመሪያው ሥዕልም ይኸው ራሱ ነበር" ማለት ይጀምራል። ሆኖም ምንም እንኳ በሥዕሉ ውስጥ ያሉት የከበሩ ድንጋዮች እነዚያው ራሳቸው ቢሆኑም ቅሉ፣ አገጣጠሙ ግን ስህተት ነበር፤ አገጣጠሙን ስላላወቀበትም እንደ መጀመሪያው የንጉሥ ሳይሆን የውሻ መልክ ያለው አድርጎ ገጣጠመው።

መናፍቃን በቅዱሳት መጻሕፍት ላይ የሚያደርጉትም ልክ እንደዚህ ነው። በመጽሐፍ ቅዱስ ያለውን ቃል ክርስቶስን እንዲያሳይ የሚያስፈልገውን ቅደም ተከተልና ጥንቃቄ ሁሉ ያፈራርሱና በራሳቸው መንገድ ሲገጣጥሙት እውነቱን ያበላሹታል፣ ይለውጡታልም። ቃላቱ፣ አገላለጾቹና ጥቅሶቹ እውነተኞች ናቸው፣ አደራደሩና አሰካኩ ግን ሐሰት ነው። በዚህ እንግዳ አደራደርና አሰካክ የሚፈጥሩት ትምህርት ለራሱ ለመጽሐፍ ቅዱስ እንግዳና ባእድ የሆነ ትምህርት ነው። (በእንተ መናፍቃን፣ 1.8.1)

ቅዱስ ሄሬኔዎስ በሌላ ምሳሌም አስረድቷል። እርሱም በዚያን ዘመን ከታዋቂው የግሪክ ባለ ቅኔ ከሆሜር መጽሐፍ የተወሰዱ ጥቅሶችን የያዘ፣ ሆኖም ጥቅሶቹ ከሆሜር መጽሐፍ ሐሳብ ዐውድ ውጭ የተጠቀሱና እንዲሁ በዘፈቀደ የተወሰዱ ጥቅሶችን አሰባስቦ ይሰራጭ የነበረ መጽሐፍ ነበር። ሁሉም ጥቅሶች በትክክል ከሆሜር መጽሐፍ የተወሰዱና የራሱ የሆሜር ነበሩ። ሆኖም በአዲሱ ዓይነት አሰዳደር (ቅንብር) የተፈጠረው አዲሱ ታሪክ ግን በምንም ሁኔታ የሆሜር ሐሳብ አልነበረም። ሆኖም በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የሆሜር ቃላትና ቅኔያዊ አገላለጾች ስላሉ ብቻ፣ መጽሐፉን የሚያነቡ ሰዎች ሆሜር ራሱ የጻፈው ታሪክ ሊመስላቸውና በቀላሉ ሊታለሉ ይችላሉ።

መጽሐፍ ቅዱስም የራሱ የሆነ አሰዳደርና ዐቅድ፣ ውሳጣዊ መዋቅርና ስምምነት አለው። መናፍቃን ይህን አሰዳደርና መዋቅር አሽቀንጥረው ይጥሉና በዚያ ቦታ የራሳቸውን ይተካሉ። በሌላ አባባል መጽሐፍ ቅዱሳዊውን ጥቅስና ትምህርት ለራሱ ለመጽሐፍ ቅዱስ ፍጹም ባዕድ በሆነ ሁኔታ ይሰድሩታል። ሆኖም በጥምቀት ጊዜ የተቀበሉትን "የእውነት ቀኖና - (the Canon of Truth)" አጽንተው የያዙ ክርስቲያኖች ግን እነዚህን ጥቅሶችና አገላለጾች ሁሉ ወደ ትክክለኛ ቦታቸው ለመመለስና በአግባቡ ለመሰደር ችግር አይኖርባቸውም። ያን ጊዜም እውነተኛውን የሥዕሉን መልክ ያያሉ ሲል ቅዱስ ሄሬኔዎስ ያስረዳል።

ይኸው አባት መጽሐፍ ቅዱስን መረዳት የሚቻለው በቤተ ክርስቲያን ውስጥ በመሆን ብቻ መሆኑን አበክሮ አስረድቷል። ከቤተ ክርስቲያን ውጭ ያሉ ግን ያ "የእውነት መለኪያ - the Canon of Truth" የላቸውም ይላል።

የፊደልም ሆነ የቃላት ቅደም ተከተላዊ አደራደር ምን ያህል ወሳኝ እንደሆነ በአንድ ቀላል ምሳሌ እንመልከት። የሚከተሉትን ሦስት የእንግሊዝኛ ፊደሎች በተለያዩ መንገዶች በመደርደር ማግኘት የምንችላቸውን ቃላቶች እንመልከት።

- **d**
- **o**
- **g**

ከእነዚህ ፊደሎች የተለያየ አደራደር የሚከተሉትን ቃላት ማግኘት እንችላለን። እነዚህም፡-

1. **dog** = ውሻ
2. **god** = ጣዖት
3. **God** = እግዚአብሔር

እንግዲህ ከእነዚህ ሦስት ፊደሎች እንኳ እጅግ የተለያዩ (ተቃራኒዎች) የሆኑትን ነገሮች አስገኝተዋል። ልዩነቱ ያለው ከፊደሎቹ ሳይሆን ፊደሎቹን ካስቀመጥንበት ቅደም ተከተልና አደራደር ነው። በአንድ መንገድ ሲደረደሩ **ውሻ** የሚል ትርጉም ያለው ቃል ይሰጣሉ። በሌላ በኩል ሲደረደሩ ደግሞ **ጣዖት** የሚል ትርጉም ያለው ቃል ይሰጣሉ። አሁንም በሌላ መንገድ ሲደረደሩ ደግሞ **እግዚአብሔር** የሚል ቃል ይሰጣሉ። የመጽሐፍ ቅዱስ አተረጓጎምም ልክ እንደዚሁ ነው። ቅዱስ ሄሬኔዎስ እንደ ገለጸው፣ ሐዋርያዊ ትውፊትን በተከተለው ቤተ ክርስቲያናዊ የአረዳድ መንገድ ሲደረደሩ የእግዚአብሔርን ሥዕል ያሳያሉ፤ "እግዚአብሔር" የሚል ቃል ይሰጣሉ። ከዚያ በወጣ መንገድ ሲደረደሩና ሲተረጎሙ ደግሞ እንደ ውሻ፣ እንደ ጣዖት ያለ የስህተት ትምህርትን ይሰጣሉ።

ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስን የሚያነብብ ሰው መጽሐፍ ቅዱስን እያነበበ ውሻ ወይም ጣዖት እንዳይመለከት ይሆን ዘንድ፣ በመጽሐፍ ቅዱስ ትምህርት እግዚአብሔርን ማየት ይችል ዘንድ ከተሳሳተ አረዳድ መጠበቅ ይኖርበታል። የመጽሐፍ ቅዱስ ዋናው ቁም ነገሩ ያለው ንባቡ ላይ ሳይሆን አረዳዱ ላይ ነውና።

በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሚገኙ ጥቅሶች አሰካክ (አደራደር) ምን ያህል መሠረታዊ እንደሆነ በአንድ ሌላ ቀላል ምሳሌም እንመልከት። እነዚህን ሦስት የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅሶች እናስታውስ፡-

- "ሄደና ታንቆ ሞተ።" ማቴ. 27፡5
- "ሂድ አንተም እንዲሁ አድርግ።" ሉቃ. 10፡37
- "የምታደርገውን ቶሎ ብለህ አድርግ።" ዮሐ. 13፡27

እነዚህ ሦስቱም ጥቅሶች መጽሐፍ ቅዱስ ላይ ያሉ ናቸው። አንድ ሰው እነዚህን ቃላት ሰካክቶ ቢያነባቸው የሚያገኘው መልእክት ምን የሚል ነው? መልእክቱ የሚሆነው "አንተም ቶሎ ብለህ ታንቀህ ሙት" የሚል ነው። ታዲያ አንድ ሰው በዚህ መልእክት መሠረት ወደ ተግባር ቢሄድ "የመጽሐፍ ቅዱስን ትምህርት እየፈጸምኩ ነው" ለማለት ይችላልን? መናፍቃን በመጽሐፍ ቅዱስ ላይ የሚያደርጉትም ልክ እንደዚህ ነው። ለሕይወት የተጻፈውን የእግዚአብሔር ቃል በተሳሳተ መንገድ ያገጣጥሟቸውና ወደ ሕይወት በመሄድ ፋንታ ወደ መታነቅ እንዲሄድ የሚያደርግ ትምህርት ያስተምሩባቸዋል። ቅዱስ ሄሬኔዎስ እንዳለው፣ ከቤተ ክርስቲያን ውጭ የሆኑ አካላት "የቅዱሳት መጻሕፍት የአረዳድ መንፈስ ቁልፉ የላቸውም - They have no key to the mind of the Scripture"። የቅዱሳት መጻሕፍትን ቃል መጥቀስ ብቻውን በቂ አይደለም፤ የመጽሐፍ ቅዱስን ቃል አጠቃላይ ሐሳብና መንፈስ በምልዐት ምን መሆኑን መረዳት ያስፈልጋል። ይህም ቅዱስ ትውፊት (Holy Tradition) የሚባለው ነው።

ቅዱስ ሄሬኔዎስ ይህን በተመለከተ እንዲህ ብሏል፡-

> መናፍቃን ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ሊጠቅሱ ይችላሉ፣ ሆኖም አተረጓጎማቸው ቤተ ክርስቲያን ከተቀበለችውና ከጠበቀችው ከቤተ ክርስቲያን የእውነት በሐዋርያዊ ትውፊት ከተቀበለችውና ከጠበቀችው ከቤተ ክርስቲያን የእውነት መርሕ ጋር የማይስማማ በመሆኑ ትምህርታቸው ስህተት ነው። (በእንተ መናፍቃን፣ 1:3:6)

ቅዱሳት መጻሕፍትን የጻፈቻቸው፣ የመረጠቻቸውና የጠበቀቻቸው ቅድስት ቤተ ክርስቲያን እስከሆነች ድረስ፣ እነዚህ ቅዱሳት መጻሕፍት እንዴት ልንረዳቸው እንደሚገባ አቅጣጫ በመስጠትና በማስተማርም ሊተካ የማይችል ወሳኝ ሚና አላት ማለት ነው። መጻሕፍቱን የመረጠቻቸውና የቀነነቻቸው ቤተ ክርስቲያን ከሐዋርያት በተቀበለችውና በተግባር በምትኖረው መርሐ እምነት መለኪያነት ስለሆነ፣ ይህን የመጻሕፍቱን መለኪያ ከእርሷ ሳይማር መጻሕፍቱን ልተርጉም ቢል

ወደ ሌላ አቅጣጫ ሊሄድ ይችላል። ይህንንም ከተፈጠሩ ጀምሮ ባለፉት አምስት መቶ ዓመታት በእያንዳንዱ የመጽሐፍ ቅዱስ ሐሳብና ጥቅስ እየተጣሉ የሚለያዩና በብዙ ሺህ የደረሱት የፕሮቴስታንት አንጃዎች በተግባር አሳይተውናል፤ "እኔን ያየህ ተቀጣ" እያሉ ናቸውና።

## 1.11 ትውፊት ምንድን ነው?

ለብዙ ዘመናት ብዙ ምዕራባውያን ጸሐፊዎች ትውፊትን የሚያዩት ላለፈ ነገር በጭፍን እንደ መገዛት እና ፡ ሕያውነት የሌለውን ያለፈ ቅርስ እንደ መጠበቅ እንደሆነ አድርገው ነበር። ስለሆነም ትውፊታዊ ቤተ ክርስቲያን ሲባል የሚመስላቸው ያረጀችና ያፈጀች፣ ወደ ኋላ የምትጎትት ዓይነት አድርገው ነበር።[89] ልጆቻቸው ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶችም ትውፊትን የሚረዱት በዚሁ በአባቶቻቸው መንፈስ ነው። ለምሳሌም "ትውፊት ወይስ ድኅነት?" በሚል ርእስ በተጻፈ የተሐድሶ መጽሐፍ ላይ ትውፊትን እተረጉማለሁ ብሎ እንዲህ ይላል፡-

- ትውፊት ማለት ግዕዝ ሲሆን በአማርኛ ሲተረጎም ደግሞ ሥርዓት፣ ደንብ፣ ከሕግ የተነሣ የሚደረግ ልማድ ወይም ወግ ማለት ነው። . . . ትውፊት በጎ ጎን ያለው ቢመስልም ነገር ግን የእግዚአብሔር ቃል ያልሆነ የእግዚአብሔርን ቃል ለመጠበቅ ሲባልም በዘመናት በተነሱ መምህራን ቀስ በቀስ እየተጨመረ የመጣ ቅብብሎሽ ነው። (ትውፊት ወይስ ድኅነት? ገጽ 1-2)

እንግዲህ ይህ የተሐድሶዎች አረዳድ በመጀመሪያ ስህተት ነው፤ ሲቀጥልም ትውፊትን በሆነው ሳይሆን ባልሆነው መረዳታቸውን የሚያሳይ ነው። ትውፊት የሚለው ቃል ሐዲስ ኪዳን በተጻፈበት እናት ቋንቋው በግሪኩ "ፓራዶሲስ - *Paradosis*" የሚለው ቃል የአማርኛ ትርጉም ነው። የቃሉ ምንጭ የሆነው ግሥ ፓራዲዶሚል - *paradidomill* የሚል ሲሆን፤ ትርጉሙም "አንድን ነገር በእጅ መስጠት ወይም ማቀበል" ማለት ነው።[90] ስለሆነም "ትውፊት" የሚለው ቃል ያልተረዱት ሰዎች እንደሚመስላቸው ኋላ ቀርነትና ኀታች አይደለም። በመጽሐፍ ቅዱስ ቋንቋ "ትውፊት" ማለት "ህብትን ማስረከብ እና መቀበል" ማለት ነው። አንደኛው ትውልድ ሐዋርያዊና ሕያው እምነትን ከእርሱ በፊት ከነበረው ይቀበላል፤ እርሱም በተራው ያንኑ የተቀበለውን ለቀጣዩ ትውልድ ያቀብላል።

---

[89] Tadros Malaty, Fr. Tradition and Orthodoxy.
[90] እንደ ላይኛው

ትውፊት ማለት ከጌታ ወይም ከጌታ ከተቀበሉት መቀበልና ያንንም በሕይወት ኖሮና ጠብቆ በተራው ለቀጣዩ ትውልድ ማስረከብ ማለት መሆኑን ቅዱስ ጳውሎስ በመጀመሪያው የቆሮንቶስ መልእክቱ፡ ሁለት ቦታ ላይ እንዲህ ሲል ገልጸልናል፡-

- "ለእናንተደግሞአሳልፌየሰጠሁትን(paradidomi)**እኔከጌታተቀብያለሁና** - (Paralarnbano)" (1 ቆሮ. 11:23)፤ እና
- "እኔ ደግሞ **የተቀበልሁትን** ከሁሉ በፊት **አሳልፌ ሰጠኋችሁ**" (1 ቆሮ. 15:3)።

የመጀመሪያው ጥቅስ ቅዱስ ጳውሎስ እርሱ የተቀበለውን ያገኘው ከጌታ መሆኑን **"እኔ ከጌታ ተቀብያለሁ"** በማለት የገለጸበት ሲሆን፤ ሁለተኛው ጥቅስ ደግሞ ያን እርሱ ከጌታ የተቀበለውን **"አሳልፌ ሰጠኋችሁ"** በማለት ለቆሮንቶስ ምእመናን መስጠቱን የገለጸበት ነው።

ጌታችን ለሐዋርያት የሰጣቸው የተጻፈ መጽሐፍ ሳይሆን ሕይወትንና የሕይወት መንገድን ነው። ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በቃሉ ያስተማረውና በተግባር ያሳየው ትምህርትና ሕይወት ሁሉም በወንጌልም ሆነ በመልእክታት ላይ አልተጻፈም። ቅዱሳን ሐዋርያት ከእርሱ የተቀበሉትን የሕይወት ትምህርትና መንገድ ሊጻፍ የሚችለውን ያህል ጻፉ። ሆኖም ሁሉም ነገር ሊጻፍ ስለማይችል ከተጻፈው ባሻገር ያለው፣ እንዲሁም የተጻፈውን ቃል የምንረዳበት የአረዳድ መንፈስ በሙሉ ተጠብቆ ያለው በቤተ ክርስቲያን ነው። ይህ ሐዋርያት ከጌታችን የተቀበሉት የሕይወት ትምህርትና ሁለንተናዊ የሆነ ክርስቶሳዊ መንገድ፣ የአኗኗሩ አጠቃላይ መንፈስ - ሁሉም - "ትውፊት" ተብሎ የሚገለጸው ነው። ማለትም ሐዋርያት ከጌታ የተቀበሉት፣ ከዚያም እነርሱም ለተከታዮቻቸው ያቀበሉት፣ እንደዚያ እያለ በቤተ ክርስቲያን በሕይወት የሚኖረውና የሚገለጠው ሁሉ **"ቅዱስ ትውፊት - Holy Tradition"** ይባላል። ይህም "ለቅዱሳን <u>አንድ ጊዜ ፈጽሞ **ስለ ተሰጠ**</u> <u>ሃይማኖት</u>" ተብሎ የተገለጸው ነው። ይሁ. 3

ኢየሱስ ክርስቶስ ትናንት ከሐዋርያት ጋር እንደ ነበረ፣ ከዚያ ቀጥሎ ከመጡት ትውልዶች ሁሉ ጋር አብሯቸው ይሠራና ይመራቸው ነበር። ለወደፊትም እስከ ዓለም ፍጻሜ ድረስ እንዲሁ አብሯቸው ይሠራል። ስለሆነም ኦርቶዶክሳዊ ትውፊት እንደ ፈሳሽ ወንዝ የሚመነጭና እንደ ኩሬ ውኃ የተቋተና የማይንቀሳቀስ ሳይሆን እንደ ፈሳሽ ወንዝ የሚመነጭና ... 

ከወደፊቱ ጋር የሚያገናኝ ሕያው ድልድይ በመሆኑ በዚህ የሕይወት ድልድይ መመላለስና መኖር ነው። ትውፊት ሕያው ነገር መሆኑን በተመለከተ የራሽያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ሊቅ የነበሩት ጆርጅ ፍሎሮቭስኪ የገለጹበት መንገድ መልካም ስለሆነ እዚህ ላይ እናስታውሰው፡-

> . . . ትውፊት የመከላከልና የመጠበቅ መርሕ ብቻ አይደለም፤ ይልቁንም በዋናነት የማደግና የዳግመኛ መወለድ መርሕ ነው። . . . ትውፊት የመንፈስ ቅዱስ የማያቋርጥ መኖር እንጂ ያለፈውን በትዝታ ማስታወስ ብቻ አይደለም።[91]

ቅዱስ ትውፊት ጠቅለል ባለ አገላለጽ ሲገለጽ የእግዚአብሔር ሕዝብ በአስተምህሮ፣ በሥርዐተ አምልኮ፣ እና በመሰል ሕይወታዊ ሂደቶች ያላቸው ቀጣይነት ያለው ሕይወት ነው።

በትውፊት የተቀበልነው ታላቅ ዋጋና ክብር ያለው መሆኑ እንደተጠበቀ ሆኖ ካለፈው የተቀበልነው ሁሉም ትክክል ነው ማለት ግን አይደለም። እኩል ዋጋ አላቸው ማለትም አይደለም። በትውፊት ከተቀበልናቸው ሀብቶች ሁሉ መጽሐፍ ቅዱስ ልዩ የሆነ ክብርና ቦታ አለው። የመጀመሪያውን ቦታ የሚይዘው እርሱ ነው። ከዚህ ቀጥሎ ደግሞ የዓለም አቀፍ ጉባኤያት አንቀጸ እምነት እና ውሳኔዎች፣ እና ሥርዐተ አምልኮ ናቸው። ከዚህ ጋር የቤተ ክርስቲያን አባቶች ትምህርቶች፣ የቅዱሳን ዜና ሕይወቶች፣ ቀኖናዎችና መሰሎች ናቸው። ሁሉም የቅዱስ ትውፊት አካል የሆኑት ነገሮች ሁሉ በአንድ ሰው አካል እንዳሉ የተለያዩ ሕዋሳት እርስ በእርሳቸው የተዋሐዱና ለአንድ ሕይወት የሚሠሩ ተገናዛቢዎች ናቸው። አንዳቸው ከሌላቸው ተነጥለው ከቤተ ክርስቲያን የሕይወት ምልዐት ውጭ የሚኖሩና የሚሠሩ አይደሉም። በአንጻሩ ምንም ያህል ጥንታዊነት ሊኖራቸው ቢችልም እንኳ ከቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ ጋር የማይስማሙ ነገሮች ደግሞ መቸም መች ተቀባይነት የላቸውም። በዚህ ረገድ ከሁለት ጽንፎች መጠበቅ ይገባል። በአንድ በኩል የቆየ ነገር ሁሉ ትክክል ነው የሚል አጉል አጥባቂነት ሲሆን፣ በሌላው ጎን ያለው ደግሞ ያለፈን ነገር ሁሉ የመናቅና ሁል ጊዜ አዲስ ነገርን የመናፈቅ አጓጉል "ዘመናዊነት" ነው።

የቤተ ክርስቲያን **ውስጣዊ ትውፊት** የተላለፈልንና ያገኘነው በሥርዐተ አምልኮ (Liturgy) ነው። ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ስለ ምስጢረ ቁርባንና ስለ ሌሎች ምስጢራት፣ ከሞት በኋላ ስላለው ሕይወትና ይህን ስለመሳሰሉ መሠረታዊ ጉዳዮች

[91] 'Sobornost: *the Catholicity of the Church*, in *The Church of God*, pp. 64-65.

የጸፈችው በጣም ጥቂት ብቻ ነው። በእነዚህ ጉዳዮች ላይ ያለው ኦርቶዶክሳዊ እምነት የሚገኘው በሥርዐተ አምልኮውስጥ ባሉት ጸሎቶችና ዝማሬዎች ነው። በቅዳሴዎቻችን፣ በቅዱስ ያሬድ የዜማ መጻሕፍት ሕያውና መሳጭ በሆነ መንገድ በጥልቀትና በምጥቀት ተጽፎ እናገኛለን። ምስጢረ ቁርባን እንዴት እንደሚከወን፣ ጥምቀት እንዴት እንደሚፈጸም፣ ሜሮን ሲቀባ ስንት ቦታ ላይና አዘገጃጀቱ እንዴት እንደሆነ፣ ይህንና ይህን በመሰሉ መሠረታዊ የድኅነት ጸጋ በሚገኝባቸው ምስጢራት ዙሪያ ያሉ ተግባራዊ ኩነቶች በዋናነት የሚተላለፉት በቃልና በተግባር ትውፊት ነው።

የትውፊት አካል የምንለው በሥርዐተ አምልኮው ውስጥ በቃላት የሚገለጹት ብቻ ሳይሆኑ እንቅስቃሴው፣ ዑደቱ፣ ቡራኬው፣ እማሬው፣ እና ይህን የመሰለው አጠቃላይ መንፈሱ ሁሉ ነው። ይህን በሕይወት ያልተቀበለ ሰው እንዲሁ መጽሐፍ ቅዱስን በማንበብ ብቻ ሐዋርያት የተቀበሉትንና አባቶቻችን የጠበቁትን ክርስትና ሊያገኘውና ሊኖረው አይችልም። የተጻፈው ትውፊት (መጽሐፍ ቅዱስ) እና ሌላው የትውፊት አካል እንደ ነፍስና ሥጋ ተዋሕዶ ነፍስ ዘርተው ሕያዋን ሆነው ሲንቀሳቀሱና ለምእመናን ሕይወትን ሰጭ ሆነው የምናገኛቸው በቤተ ክርስቲያን ሥርዐተ አምልኮ ውስጥ ነው።

## 1.12 መጽሐፍ ቅዱስ እና ቅዱስ ትውፊት

ፕሮቴስታንቶች ስለ ትውፊት ካላቸው የተሳሳተ አረዳድ አንደኛው ትውፊትን ከመጽሐፍ ቅዱስ **የተለየ የሆነ ሌላ ዓይነት መገለጥ** አድርገው ማሰባቸው ነው። ሆኖም ትውፊት ማለት ከመጽሐፍ ቅዱስ የተለየ መገለጥ ሳይሆን ጌታችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በቃሉ እየተናገረና በተግባር እያደረገ ያስተማረው ትምህርትና የሰጠው ሕይወት በሙሉ ከሐዋርያት ለቀጣዩ ትውልድ፣ ከዚያም ለቀጣዩ በቅብብሎሽ የተላለፈው በምልዐት ያለበት ሕይወት ማለት ነው። ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስ (የተጻፈው የጌታ ትምህርት) የትውፊት አካል ነው። ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስ እና ትውፊት እንደ ሁለት ተፎካካሪ ምንጮች የሚታዩ ሳይሆኑ አንድ የሆነው የክርስትና ሕይወት የተላለፈባቸውና የተጠበቀባቸው መንገዶች ናቸው።

የክርስትና አስተምህሮና ሥርዐተ አምልኮ ሁሉም ነገሩ በጽሑፍ የመጣልን አለመሆኑን ከላይ ተመልክተናል። ለዚህ ነው ታላቁ አባት ቅዱስ ባስልዮስ ዘቂሣርያ "እንዳንዶቹን ነገሮች ያገኘናቸው ከተጻፈ ትምህርት [ከመጽሐፍ] ነው፣ ሌሎቹን ደግሞ ያገኘናቸው በምስጢራት ለእኛ ከተላለፈልን ሐዋርያዊ ትውፊት ነው፤ እነዚህ

ሁለቱም በነገረ ሃይማኖት ላይ ያላቸው ሥልጣን እኩል ነው (the same force)[92] ያለው።

ስለዚህ ትውፊት ስንል ያልተጻፉ ነገሮችን ብቻ ሳይሆን የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍትን፣ በዓለም አቀፍ ጉባኤያት የተወሰኑ አንቀጸ እምነቶችን፣ የአባቶቻችንን አስተምህሮዎች፣ የሥርዐተ አምልኮመጻሕፍትንና ተግባራዊ ሕይወታዊ አተገባበርን፣ ቅዱሳት ሥዕላትን ሁሉ የሚያጠቃልል ሰፊ ነገር ነው። ራሱ መጽሐፍ ቅዱስን ሳይቀር ያገኘነው በትውፊት መሆኑን ከላይ ስለ መጽሐፍ ቅዱስ ቀኖና ስናነሣ ተመልክተናል። ብዙውን ጊዜ ትውፊት ሲባል "በጽሑፍ ያልተመዘገበው የክርስቶስ ትምህርት" ተብሎ የሚገለጽ ቢሆንም ቅሉ ይህ ግን ጠባብና ውስን የሆነ አገላለጽ ነው። ይህ ዓይነቱ የትውፊት ትርጉም መጽሐፍ ቅዱስንና ትውፊትን እንደ ሁለት የክርስትና አስተምህሮ ምንጮች አድርጎ ወደ ማየት እንዳይወስድ ጥንቃቄ ይፈልጋል። ምክንያቱም የክርስትና ምንጩ አንድ ነው፤ እርሱም እግዚአብሔር ነው። ከእርሱ የተገኘውን አስተምህሮ ቅዱሳን ሐዋርያት ተቀበሉ፣ ከዚያም ከጌታ የተቀበሉትን የተወሰነውን በመጽሐፍ ጽፈው አስተላለፉልን፣ ቀሪውን ደግሞ በቃልና በተግባራዊ ሕይወት አስተላለፉልን።

ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስ የትውፊት አካል ነው። በመሆኑም ትውፊት አንድ ነገር፣ መጽሐፍ ቅዱስ ደግሞ ሌላ ነገር ሳይሆኑ መጽሐፍ ቅዱስ የሐዋርያዊው ትውፊት አካል ነው። ትውፊት እናት ሲሆን መጽሐፍ ቅዱስ ደግሞ ደገኛው የትውፊት ልጅ ነው።

ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ከትውፊት መካከል ለመጽሐፍ ቅዱስ የተለየ ቦታና ክብር አላት። ቅዱስ ወንጌል በቤተ ክርስቲያኑ ውስጥ ሲቀመጥና ሲነበብ ልዩ ክብር አለው። ከተነበበ በኋላም ከፍቅርና ከአክብሮት የተነሣ እንሳለመዋለን። የቤተ ወንጌል ይቀመጣል። በጸሎተ ቅዳሴ ጊዜ በመንበር ላይ በልዩ ክብር ቅዱስ አክብረው ተሸክመውት ይዞራሉ። ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን የእግዚአብሔርን ቃል ለያዘው ለመጽሐፍ ቅዱስ ያላት አክብሮትና ፍቅር በቃላት ሊገለጽ አይችልም። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን የፈጠራ ትምህርት የማትቀበልበት አንዱ ምክንያትም ለመጽሐፍ ቅዱስ ልዩ ክብር ያላት ስለሆነ ነው።

የመጽሐፍ ቅዱስን ቃል ስንረዳና በተግባርም ሆነ በቃል ስንተረጉም የራሳችንን አረዳድና ስሜት ተከትለን እንዳንሄድ የሚጠብቀን ከሐዋርያት ጀምሮ የነበረችው ቤተ

92 ፀሐንተ መንፈስ ቅዱስ፡ ምዕ.66

ክርስቲያን የተረዳችበትንና የኖረችበትን ስንረዳ ነው። ትውፊት ማለት ይህ ነው። ክርስትና በየዘመናቱ የሚለወጥ እንዳለመሆኑ የቀደሙ አባቶቻችን ከእግዚአብሔር ጋር የኖሩበትን የተቀደሰ መንገድ መቀበልና መኖር ነው። ትውፊት በክርስትና ሕይወት መንገድ የነበረውንና ያለውን ነገረ ክርስትና በሙሉ ሳይበረዝና ሳይከለስ ትኩስና ሕያው አድርጎ ከዛሬ ጋር የሚያገናኝ፣ የዛሬውንም ለነገ የሚያስረክብና በዚህም የየትኛውም ዘመን ትውልድ ከሐዋርያትና ከጌታ ጋር ያልተቋረጠ ግንኙነት እንዲኖረው የሚያደርግ የአንዲቷ ቤተ ክርስቲያን የሕይወት ወንዝ ፍሰት ነው።

ቤተ ክርስቲያን የብሉይ ኪዳን እና የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን የሰበሰበቻቸው፣ ከሌሎች መጻሕፍት የለየቻቸው፤ ከዚያም የብሉይና የሐዲስን መጻሕፍት የእግዚአብሔር እስትንፋስ መሆናቸውን የተረዳችውና የተቀበለችው በትውፊት ነው። ይህ መረዳት የነበረውም የመጻሕፍት ቀኖና ከመወሰኑ በፊት ነው። ይህ የሆነውም ትምህርቱና ተግባራዊ ሕይወቱ በቤተ ክርስቲያን ከሐዋርያት ጀምሮ ከትውልድ ወደ ትውልድ ይፈስ የነበረ ሕያው ጅረት - ትውፊት - ስለነበር ነው።

እግዚአብሔር ለሰዎች ያደረገውን አምላካዊ መገለጥ በመጠበቅ ረገድ የቃል ትውፊት ከመጽሐፍ ቀደምትነት አለው። ከሙሴ በፊት መጽሐፍ አልነበረም። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ለደቀ መዛሙርቱ ያስተማራቸው በቃልና በተግባር እያደረገ በአርአያነት በማሳየት ነበር። ቅዱሳን ሐዋርያትም መጀመሪያ ላይ ያደረጉት እንደዚሁ ነበር፣ ማለትም ወንጌልን ለመስበክ ሲሰማሩ መጀመሪያ መጽሐፍ ጽፈው ከዚያ በኋላ አልነበረም ወደ ማስተማር የሄዱት። ትውፊት መጽሐፍ ቅዱስን በተጻፈበት መንፈስና ዓላማ እንድንረዳው ከፊት ሆኖ የሚመራን መሪ ነው። እንደዚሁም ትውፊት በቅዱስ መጽሐፍ የተጻፉትን የሕይወት ምስጢራት ጌታችን ለደቀ መዛሙርቱ ባሳያቸውና እነርሱም ሲፈጽሙ በነበረበት መንገድ እንድንፈጽም ተግባራዊ ቅብብሎሹን የሚያሳይ፣ እና በክርስትና ሕይወት ውስጥ የሚፈጸሙና ተግባራዊ ቅብብሎሹን የሚያሳይ፣ እና በክርስትና ሕይወት ውስጥ የሚፈጸሙና ሲተገበሩ የነበረው ጥንተ የሚከወኑ ነገሮችን ሁሉ በጌታና በሐዋርያት ሲጀመሩና ሲተገበሩ የነበረው ጥንተ መልካቸውና መንፈሳቸው ሳይለወጥና ሳይበረዝ እንዲከወንና እንዲጠበቅ የሚያደርግ ነው። ስለሆነም ከአምላካዊ መገለጥና ከመጽሐፍ ቅዱስ ጋር የተስማማ እስከሆነ ድረስ ትውፊት ሊጠበቅ ይገባዋል።

ትውፊት ከመጽሐፍ ቅዱስ የተለየ መገለጥ አይደለም፣ የክርስትና ሌላ ሁለተኛ የትምህርት ምንጭም አይደለም። መጽሐፍ ቅዱስ የቤተ ክርስቲያን ሀብት ነው እንጂ የግለሰቦች ሀብት አይደለም። ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ይህን መጽሐፍ የምትረዳበትና በተግባር የምትተረጉምበት መንፈስ ትውፊት ነው። ከዚህ መንፈስ ውጭ ማንም ሰው በየግሉ አረዳድ ልረዳው ልተርጉመው ቢል ውጤቱ በፕሮቴስታንቱ

ዓለም ከመጀመሪያ ጀምሮ እንደ ታየውና ዛሬም በየቀኑ እንደሚታየው ያለ ነው የሚሆነው።

ስለዚህ ትውፊት መጽሐፍ ቅዱስን ስናነብና ስንረዳ ሊኖረን የሚገባው ቤተ ክርስቲያናዊ መንፈስ (The Mind of the Church) ነው። ስለሆነም ትውፊት በመጽሐፍ ቅዱስ ከተጻፈው የእግዚአብሔር ቃል ላይ ሌላ ነገር ልጨምር የሚል ሳይሆን ያ የተጻፈው ቃል የተጻፈበትን ዐውድና መንፈስ፣ አተገባበርና አፈጻጸም፣ አተረጓጎምና አረዳድ የሚመራ አቅጣጫ ጠቋሚ (ኮምፓስ) ነው። ቅዱስ ሄሬኔዎስ በምሳሌ እንዳስረዳው ያንኑ የከበረ ማዕድን የሆነውን የእግዚአብሔር ቃል እኔስ ከማን አንሳለሁ በሚል ስሜት በግምትና በድፍረት ባልሆነ መንገድ በመገጣጠም የንጉሥ ሥዕል ሳይሆን የውሻ ሥዕል እንዲመስል ከሚያደርግ ስህተት የሚጠብቅ ነው። መጽሐፍ ቅዱስን ስናነብና ስንማር ሁል ጊዜም ጥቅሶችንና ሐሳቦችን የምንረዳውና የምንደረድረው ንጉሥ ክርስቶስን በሚያሳይ መንገድ እንዲሆን የሚረዳና የሚመራ ነው። ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስ የተሰጠውም የሚጠበቀውም በትውፊት ነው። ትውፊትና መጽሐፍ ቅዱስ የአንድ ሳንቲም ሁለት ገጽታ የሆኑና የማይነጣጠሉ ናቸው።

ስለዚህ ትውፊት ከወንጌል ጋር የሚፎካከር፣ ወይንም ደግሞ ለምርጫ እንደሚቀርቡ ሁለት አማራጮች የሚታይ ሳይሆን በመጽሐፍ ከተጻፈልን የእግዚአብሔር ቃል ጋር በአንድነት ሆኖ የክርስቶስን ትምህርትና ተግባራዊ ሕይወት ከትውልድ ወደ ትውልድ ሲያሸጋግር የኖረና ያለ፣ ወደፊትም የሚቀጥል ድልድይ ነው። ቤተ ክርስቲያን በመጽሐፍ የተጻፈውን የተቀበለችው በሥርዐተ አምልኳዊ ሕይወቷ በቃል ሲሰበክና በሕይወት ሲተገበር ከነበረው - ከትውፊት - ጋር የተስማማና እርሱን የሚገልጥ ስለሆነ ነበር። በአንጻሩ ደግሞ በሐዋርያት ስም የተጻፉና የተሰራጩ የተለያዩ መጻሕፍትን ያልተቀበለቻቸው ከጌታ ከተቀበለችውና በሥርዐተ አምልኮ ሕይወቷ ከምትኖረውና ከምታምነው - ከትውፊቷ - ጋር የማይስማማና ተቃራኒ ስለሆነ ነበር። ስለሆነም ትውፊት የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት የተጻፉበት፣ ከሌሎች መካከል ተለይተው የተመረጡበትና የተጠበቁበት ነው። ከጌታችን ዕርገት ከዓመታት በኋላ ቤተ ክርስቲያን የተጻፈ ወንጌል ሲኖራትም ከዚያ በፊት ስታስተምረውና ስትኖረው ከነበረው አንድም ነገር አልቀየረችም፤ የተጻፈውን አጽንታ በቃል ሲሰበክ ከነበረው ጋር ስትጠቀምበት ኖረች እንጂ።

በብዙዎቹ የምዕራባውያን ሰዎች ዘንድ ግን ትውፊትን ከመጽሐፍ ቅዱስ ጋር ለምርጫ እንደ ቀረቡ እንደ ሁለት ተፎካካሪ አማራጮች አድርገው የማየት ዝንባሌያቸው ሥር የሰደደ ነው። ብሩስ የተባለ የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት ፕሮፌሰር ይህን በተመለከተ እንዲህ ብሏል፡- "ምዕራባውያን ክርስቲያኖች 'መጽሐፍ ቅዱስን

እና 'ትውፊትን' እርስ በእርሳቸው እንደሚቃረኑና ከሁለት አንዱ ብቻ መመረጥ እንዳለበት ተፎካካሪ አማራጮች አድርገው የማየት አባዜ አለባቸው።"[93]

ሆኖም ወንጌል የትውፊት አካል ነው እንጂ ከትውፊት የተለየ ባእድ ነገር አይደለም። ምክንያቱም በወንጌል ላይ የተጻፈው በትውፊት ከነበረው መካከል ሊጻፍ የሚቻለውና የሚገባውም ብቻ ነውና። ሁለቱም የሚሰብኩት አንድን እውነት ነው።

## የመጻሕፍት መጻፍ ትውፊትን አላስቀረውምን?

የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት መጻፍ የቃል ትውፊትን አላስቀረውም ወይ? ብሎ የሚጠይቅ ሊኖር ይችል ይሆናል። መልሱ አላስቀረውም ነው። የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን የጻፉት ራሳቸው ሐዋርያት ክርስቲያኖች የተጻፈላቸውን ቃል ብቻ ሳይሆን በቃል የተማሩትንም ሊጠብቁ እንደሚገባ ደጋግመው አስተምረዋል። ለምሳሌም ቅዱስ ዮሐንስ ወንጌላዊ በሁለተኛ መልእክቱ ላይ እንዲህ ብሏል፡-

> እንድጽፍላችሁ የምፈልገው ብዙ ነገር ሳለኝ በወረቀትና በቀለም ልጽፈው አልወድም፤ ዳሩ ግን ደስታችሁ ፍጹም እንዲሆን **ወደ እናንተ ልመጣ፤** አፍ ለአፍም ልናገራችሁ ተስፋ አደርጋለሁ። 2 ዮሐ. 12

እንዲሁም ይኸው ሐዋርያ በሦስተኛ መልእክቱ ላይ እንዲህ ብሏል፡-

> ልጽፍልህ የምፈልገው ብዙ ነገር ነበረኝ፤ ዳሩ ግን በቀለምና በብርዕ ልጽፍልህ አልወድም፤ ነገር ግን ወዲያው ላይህ ተስፋ አደርጋለሁ፤ አፍ ለአፍም እንነጋገራለን። 3 ዮሐ. 13-14

ቅዱስ ጳውሎስም "የቀረውንም ነገር በመጣሁ ጊዜ አደነግጋለሁ" በማለት መልእክት መጻፉ ሁሉንም ነገር በመልእክቱ በጻፈው ቃል ብቻ የጨረሰው አለመሆኑን ገልጿል። ይልቁንም በአካል ሲሄድ የሚደነግግላቸውን ነገር እንዲጠብቁ አስቀድሞ በመልእክቱ አሳሰባቸው እንጂ ከጻፍኩላችሁ በቀር ሌላ አንዳችም ነገር እንዳትቀበሉ አላላቸውም። እንደዚሁም ደቀ መዝሙሩን ቲቶን በመልእክቱ እንዲህ ብሎታል፡- "ስለዚህ ምክንያት **የቀረውን እንድታደራጅ** በየከተማውም፤ እኔ አንተን እንዳዘዝሁ፤ ሽማግሌዎችን እንድትሾም በቀርጤስ ተውሁህ" ቲቶ 1፡5 "የቀረውን እንድታደራጅ" ማለት ምን ማለት ነው? ከጻፍኩልህ ውጭ ሌላ ነገር የለም ማለት ነው? በጭራሽ! በመልእክት ከጻፈለት ባሻገር ያሉ የእርሱ ደቀ መዝሙር ለሆነና ከእርሱ በቃል ብቻ ሳይሆን በተግባርም ለተማረ ደቀ መዝሙር እንደሚገባ ያደርግና ቤተ ክርስቲያንን በትምህርትና በሥርዐተ አምልኮ ያደራጅ ዘንድ መከረው እንጂ።

---

[93] F. F. Bruce: *Tradition: Old and New*, p. 37

የትውፊት ሚናና አስፈላጊነት የተነሣው በዚያ ዓይነቱ መሠረታዊና ታሪካዊ ሁኔታ ላይ ነበር።

እነዚያን መናፍቃን ስህተታቸውን በማጋለጥና እውነተኛውን ሐዋርያዊ ትምህርት በመጠበቅ ረገድ ታላቅና እጅግ ውጤታማ ሥራ የሠራው የቅዱስ ፖሊካርፐስ ደቀ መዝሙር የነበረው ቅዱስ ሄሬኔዎስ ነው። ቅዱስ ሄሬኔዎስ የግኖስቲኮችን ስህተቶች ከሥር ከመሠረቱ አንጥሮ በማሳየት፣ ከዚያም ትምህርታቸውን በብሉይ ኪዳንና በሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት በመመዘን መያዣ መጨበጫ ያልነበረውን የግኖስቲኮችን ፈጠራዊ ኑፋቄ ለአንዴና ለመጨረሻ እንዲያገግም አድርጎ የቀበረው እርሱ ነው።

**ቅዱስ ሄሬኔዎስ ስለ ትውፊት ያስተማረው ጠቅለል ሲል እንዲህ የሚል ነው፡-**

1. **የተቀበልነው የክርስትና እምነት አስተምህሮ - የተጻፈንም ሆነ በቃል የተላለፈን ሁሉ የሚወክል ነው።**

ከሐዋርያት የተገኘው ትውፊት፣ በቤተ ክርስቲያን ባሉ ከሐዋርያት ጀምሮ ሳይቋረጥ በመተካካት በመጡትና ባሉት ጳጳሳት የተላለፈና የተጠበቀ ነው። ሐዋርያዊ ትውፊት የሚጠበቀው፣ የሚወረሰውም በሐዋርያዊ ቅብብሎሽ ነው ይላል።[97] ይህን በተመለከተ እንዲህ ይላል፡-

- ሐዋርያት ትምህርታቸውን በመጽሐፍ ጽፈውልን ባይሆን ኖሮ ምን እናደርግ ነበር? እነርሱ አብያተ ክርስቲያንን አደራ ለሰጧቸውና ላስጠበቋቸው፣ እና በቦታቸው ለተኳቸው አባቶች የሰጡትን የትውፊት መንገድ መከተል አይገባንም ነበርን?[98] (3:4:1)
- በዚህ ቅደም ተከተልና በዚህ ውርርስ ቤተ ክርስቲያናዊው ትውፊትና የእውነት ትምህርት ከሐዋርያት ወደ እኛ መጥቶልናል። አንድና አንድ ዓይነት የሆነ ሕይወትን ሰጪ እምነት ከሐዋርያት አንስቶ እስከ አሁን በቤተ ክርስቲያን እየተጠበቀ ለመኖሩና በእውነት የተላለፈልን ለመሆኑ ዋናው ማረጋገጫው ይህ ትውፊት ነው። (3:3:3)
- በቤተ ክርስቲያን በሐዋርያት መንበር ያሉትን አባቶች መታዘዝ

[97] Irenaeus: *Against heresies* 3:2:2, 3:3:1, 3:4:1.

[98] "For how should it be if the Apostles themselves ***had NOT left us their writings***? Would it not be necessary to ***follow the course of the TRADITION which they handed down*** to those whom they did commit the Churches?"

ይገባል። . . . እነርሱ ከኤጺስ ቆጶስ መንበር መወራረስ ጋር የእውነትን ጸጋ አብረው የተቀበሉ ናቸውና። (4:26:2)

2. ሐዋርያዊ ትውፊት ስውር የሆነ ነገር ሳይሆን እውነትን ለመቀበልና ለማወቅ ለሚፈልጉ ሁሉ ክፍት የሆነና ሊያውቁት የሚችሉ ነው። በዓለም ሁሉ ባሉ አብያተ ክርስቲያን ዘንድ የተገለጠና የታወቀ ነው።[99]

    - የሐዋርያት ትውፊት [ግኖስቲኮች ከሚሉት] በተቃራኒ በዓለም ሁሉ የተገለጠና የታወቀ ነው፣ እውነቱን ለሚያዩ ሁሉ በእያንዳንዱ ቤተ ክርስቲያን ክፍት ነው። . . . (3:1 ፤ 3:3)

3. ሐዋርያዊ ትውፊት መጽሐፍ ቅዱስን በትክክለኛው መንገድ የምንረዳበት የአረዳድ መንገድ ነው። መጽሐፍ ቅዱስን ስናነብ ሊኖረን የሚገባው ቤተ ክርስቲያናዊ ሕሊና ነው።

    - መናፍቃን የመጽሐፍ ቅዱስን አንድነት እውቅና ሳይሰጡና ሳይጠነቀቁ፣ የተለያዩ ጥቅሶችን ነጥለው በመጥቀስና ለራሳቸው ሐሳብ በሚመቻቸው መንገድ እንደገና በመሰካካት መጽሐፍ ቅዱስን በተሳሳተ መንገድ ተርጉመውታል፣ ሐሳቡን አጣምመውታል። ገጸ ንባቦቹን ተጠቅመውባቸዋል፣ ሆኖም በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሆነው ስለማያነቧቸውና ስለማይረዷቸው በሐዋርያት ትውፊት መሠረት አያነቧቸውም። ትክክለኛው የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድ ያለው ቅዱስ ትውፊት ባለባትና ሐዋርያዊው አስተምህሮ ተጠብቆ በሚገኝባት በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ብቻ ነው። . . . መናፍቃን ግን . . . ከቅዱሳት መጻሕፍትም ጋር ሆነ ከትውፊት ጋር አይስማሙም። (1:8:1 ፤ 5:20:2 ፤ 3፡2፡1)

ከግኖስቲኮች ጋር ከባድ ትግል ላይ የነበሩት ቅዱስ ሄሬኔዎስና ሌሎቹም ኦርቶዶክሳውያን አባቶች መጽሐፍ ቅዱስን ልንረዳውና ልንተረጉመው የሚገባው ሐዋርያት ከጌታ እንደ ተቀበሉትና እነርሱም ለተከታዮቻቸው እንዳስተማሩት የትምህርትና የሕይወት መንፈስ ሊሆን እንደሚገባ አበክረው ያስተምሩና ያሳስቡ ነበር።

መጽሐፍ ቅዱስ የተጻፈው ይህን የቤተ ክርስቲያን እምነትና ሕይወት ለመግለጥ፣ ለመጠበቅና ለማስረዳት ነው። ስለሆነም መጽሐፍ ቅዱስን ለመረዳት በመጀመሪያ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ መኖርና መጽሐፉ ሊገልጠውና ሊያስረዳው የሚሻውን

[99] እንደ ላይኛው 3:3:1.

ጭብጥ ነገር ማወቅ የግድ ይላል። ከቤተ ክርስቲያን ሐዋርያዊና ሕያው ከሆነው ሕይወታዊ ትውፊቷ ውጭ የሆኑት ግን ይህ የወንጌል ልብና ማዕከል የሆነው ነገር ሳይኖራቸው ቀሩ። ለእነርሱ መጽሐፍ ቅዱስ ማለት እንዲሁ በየምዕራፉና ቁጥሩ ያሉት ጥቅሶች እንዴት እንደሚዛመዱ በትክክል የማያውቋቸው የጥቅሶችና የምዕራፎች ስብስብ ነው። ስለሆነም እነዚህን ጥቅሶች እነርሱ በሚመስላቸው በራሳቸው አረዳድ ለመሰደርና ለማስቀመጥ ይሞክራሉ። ያን ጊዜ መጽሐፍ ቅዱስ ከሚለው እምነት የተለየና ተቃራኒ የሆነ "ሌላ እምነት" ይፈጥራሉ።

በዘመነ ሐዋርያውያን አበውና ከዚያም ቀጥሎ በነበሩት ዘመናት የነበሩት አባቶቻችን መጽሐፍ ቅዱስን እየጠቀሱ ነገር ግን ከመጽሐፍ ቅዱስ መሠረታዊ ጭብጥና ትምህርት ተቃራኒ የሆነ ነገር ይዘው እየተነሡ ያውኩ ከነበሩ መናፍቃን ጋር በሚያደርጓቸው ተጋድሎ ዋና ነጥባቸው፡ መናፍቃን የቤተ ክርስቲያን **"መርሐ እምነት -** Rule of Faith - *"regula fidei"*" የላቸውም የሚል ነበር። ጠርጠሉስ የተባለው ሊቅ ከሐዋርያዊው እምነት አንድነት ከሌላቸው ከመናፍቃን ጋር መጽሐፍ ቅዱስን አልነጋገርም ይል ነበር። ምክንያቱም መጽሐፍ ቅዱስ የቤተ ክርስቲያን ሀብት ነው እንጂ የእነርሱ ምናቸውም አይደለምና።

አንድ ሰው መጽሐፍ ቅዱስን በአግባቡ ለመረዳት ይችል ዘንድ መጽሐፉን ከማንበቡ በፊት የቤተ ክርስቲያንን "መርሐ እምነት" ማወቅን ሊያስቀድም ይገባል በማለት አጥብቆ ያስረዳ ነበር። ለመጽሐፍ ቅዱስ ቁልፉ ይህ ነው፡ እውነተኛ ለሆነ መጽሐፍ ቅዱሳዊ አተረጓጎም ምትክ የሌለው ቅድመ ሁኔታው ይህ ነው። የቤተ ክርስቲያን ትውፊት ወይም "መርሐ እምነት" ለቅዱሳት መጻሕፍት ትክክለኛ አተረጓጎም ቁልፍ ነው ይል ነበር። መናፍቃን ይህ "መርሐ እምነት" ስለሌላቸው መጽሐፍ ቅዱስን እነርሱ እንዲሉላቸው የሚፈልጉትን ነገር እንዲል ያደርጉታል ይላል።[100]

ይህ "መርሐ እምነት" የተገኘው ከሐዋርያት የቃል ትምህርትና ተግባራዊ የሕይወት ምሳሌነት ነው። እንዲሁም ጌታ ያሳያቸውን ምስጢራት ሲፈጽሙና ሲከውኑ በተግባር ካሳዩትና ከኖሩት ነው። የቅዱሳት መጻሕፍት ዋናው ጭብጣቸውና ነገራቸው ይህ ነው። አንድ ሰው ይህን ሳይረዳ እንዲሁ መጽሐፍ ቅዱስን በማንበብ ብቻ የመጽሐፍ ቅዱስን ጭብጥ አውቃለሁ ብሎ ቢነሣ የራሱን ግለሰባዊ አረዳድና እምነት ላለመፍጠሩ ዋስትና አይኖርም። እንኳንስ ረቂቅ የሆነውን የእግዚአብሔር ቃል ይቅርና የአንድን ጭብጥ ያለው መጽሐፍ እንኳ ሐሳቡን በትክክል ለማግኘትና ለመረዳት የሚያስፈልጉ ነገሮች አሉ።

100 Cf. De praescrip 9, De Resurr. 21, Adv. Prax. 26.

እንዲቷ የክርስቶስ ቤተ ክርስቲያን መጻሕፍቱን የምትረዳበትና የምትተረጉምበት መንገድ አንድ ሆኖ ሳለ፣ መናፍቃኑ የሚረዱበትና የሚተረጉሙበት መንገድ ግን እንደየግለሰቦቹ ብዛት የተለያየና የአንዱ ከሌላው የሚጣላ ነበር። ይህ ለምን ሆነ ሲባል የቤተ ክርስቲያን "መርሐ እምነት" ሳይኖራቸው በራሳቸው ግላዊ አረዳድና ከተለያዩ አስተሳሰቦችና ፍልስፍናዎች በቀዱቸው መለኪያዎች በመመራት እንረዳው እንተርጉመው ስላሉ ነበር። በቅድስት ቤተ ክርስቲያን በትምህርቷና በሥርዐተ አምልኮዋ ከሚታመነውና ከሚኖረው ከዚህ የቤተ ክርስቲያን "መርሐ እምነት" - Rule of Faith" ውጭ በሌላ መንገድ መጽሐፍ ቅዱስን ልተርጉም ቢባል መጽሐፍ ቅዱስ በተሳሰተ መንገድ ይተረጎማል እንጂ ከዚያ ውጭ ሊሆን አይችልም ሲሉ ቅዱስ ሄሬኔዎስና ጠርጠሉስ አበክረው ያስረዳሉ።[101]

ስለዚህ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ዘንድ ትውፊት ከሁሉም በፊት መጽሐፍ ቅዱስን ለመረዳትና ለመተርጎም የሚያስፈልግ መርሕ እና ሰው በመጽሐፍ ቅዱስ ባሕር ውስጥ ገብቶ ሰጥሞ እንዳይቀር የትርጓሜ መርከብን የሚመራ መልህቅ ነበር። ትውፊት በመጽሐፍ ቅዱስ የተገለጠውንና የተጻፈውን የሕይወት ቃል ለመረዳት የሚያስችለውን ሕያው ዐውድና መንፈስ የሚሰጥ ነበር። የክርስትና እውነት በቅዱስ ሄሬኔዎስ አገላለጽ "በጽኑ ዐለት ላይ የተመሠረተና ወጥነት ያለው የእውነት አካል - well-grounded system, a *corpus veritatis*" ወይም ደግሞ መሳጭ የሆነ አንድ ጣዕመ ዜማን የሚሰጥ የተለያዩ አውታሮች ኅብረ ድምፅ - a "harmonious melody" ነው። አንድ ሰው መጽሐፍ ቅዱስን ሲያነብ በየመጻሕፍቱ ውስጥ ይህን አንድ የሆነ ጣዕመ ዜማ (አንድ የሆነውን የክርስትና እውነት) የማይሰማ ከሆነ የዜማ አውታሮቹን አመታት አላወቀበትም ማለት ነው። ይህን የክርስትና እውነት ስምምነትና አንድነት ለመረዳት የሚቻለው ከሁሉ አስቀድሞ በእምነት ነው።

### 1.13.2 ትውፊት በ4ኛው መቶ ዓመት

በ4ኛው መቶ ዓመት የነበረው ሁኔታም ከዚያ በፊት ከነበሩት ሁኔታዎች ብዙም የተለየ አልነበረም። ከአርዮሳውያን ጋር የነበረው ልዩነትና ክርክር መሠረቱ የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳድና አተረጓጎም ልዩነት ነበር። አርዮሳውያን የክህደት ትምህርታቸውን ይነዙ የነበረው የፈጠራ ትምህርታቸውን ይደግፉልናል በሚሉት መንገድ ከብሉይና ከሐዲስ ብዙ ጥቅሶችን በመደርደር ነበር። የመጽሐፍ ቅዱስ አረዳዳቸውና አተረጓጎማቸው በአብዛኛው ከእነርሱ በፊት ከነበሩ መናፍቃን ጋር ተመሳሳይ ነበር። እርሱም የቤተ ክርስቲያንን የአረዳድ መንፈስ - ትውፊት -

[101] Georges Florovsky, *Scripture and Tradition*: pp.288-293.

ትተው በራሳቸው የአረዳድ መንገድ መንጎድ ነበር። አካሄዳቸው ሁሉ እግዚአብሔር ለገለጠው እውነት አጠቃላይ በሆነ አረዳድ ላይ የተመሠረተ ሳይሆን የተወሰኑ ጥቅሶች ላይ ብቻ ከመጠን በላይ የሆነና ያልተመጣጠነ ትኩረት በማድረግ ነበር።[102] አስቀድመው የቤተ ክርስቲያንን "መርሐ እምነት" ገንዘብ ሳያደርጉ በራሳቸው የግል አረዳድ፣ በተለይም ደግሞ በዘመኑ ከነበረው የፍልስፍና አስተሳሰብ እርሾ ጋር ቀላቅለው እንረዳው በማለታቸው ከእውነተኛው የሕይወት መንገድ ወጡ።

በዚያን ጊዜ ሁኔታ ኦርቶዶክሳውያን ክርስቲያኖች ይግባኛቸው የቤተ ክርስቲያን የአረዳድ መንፈስ፣ ማለትም "መርሐ እምነት - Rule of Faith" ነበር። የቅዱስ አትናቴዎስ ሐዋርያዊ ዋናው ትኩረቱና ስልቱ ይህ ነበር። ከአርዮሳውያን ጋር በነበረው ክርክር ከእርሱ በፊት የነበሩት አባቶች እንዳደረጉት ሁሉ እርሱም ደግሞ ደጋግሞ የ "መርሐ እምነት - Rule of Faith" ምስክርነት አስፈላጊ መሆኑን በአጽንኦት ያነሣ ነበር።

ለቅዱስ አትናቴዎስ መጽሐፍ ቅዱስ በእግዚአብሔር መንፈስ የተጻፈና በቂ የሆነ የአስተምህሮ ምንጭ ነው። ሆኖም ሕያው በሆነው ሐዋርያዊ የቤተ ክርስቲያን ትውፊት ዐውድ መሠረት፣ በ "መርሐ እምነት - Rule of Faith" መሪነትና መንፈስ መተርጎም ግን አለበት ይላል።

ሆኖም ከላይ እንደ ተመለከትነው ይህ "መርሐ እምነት" በሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ውስጥ የተጻፈው የሐዋርያት ስብከት ጭብጥ ሓሳብ ነው እንጂ በመጽሐፍ ቅዱስ ላይ የሚጫን ሌላ ውጫዊ ወሳኝ አካል አይደለም። ቅዱስ አትናቴዎስ "ጌታ የሰጠውን፣ ሐዋርያት የሰበኩትን፣ አባቶቻችን የጠበቁትን የሐዋርያዊቷን ቤተ ክርስቲያን ትውፊት፣ ትምህርትና እምነት ከመጀመሪያው እንመልከት"[103] ይላል።

**ቅዱስ አትናቴዎስ እና "ነጽሮተ እምነት - τον σκοπον - Scope of Faith"**

ኦርቶዶክሳውያን አባቶች ታሳቢ የሚያደርጉት ነገር የቤተ ክርስቲያንን የአረዳድ መንፈስ (The mind of the Church)፣ እና አንድ ጊዜ የተሰጠውንና በቤተ ክርስቲያን የተጠበቀውን እምነት ነው። የቅዱስ አትናቴዎስ ዋና ትኩረቱና ስልቱም ይህ ነበር። ማለትም መጽሐፍ ቅዱስ ሲነበብና ሲተረጎም ቤተ ክርስቲያን የተቀበለችውንና የጠበቀችውን እምነት በሚጠብቅና በሚያጸና መንገድ እንጂ ከዚህ ጋር በሚቃረን

---

[102] ዮሐ. 14፥28 እና ምሳ. 8፥22 የአርዮሳውያን ተወዳጅ ጥቅሶች ነበሩ። ልክ እንደ ዘመናችን ፕሮቴስታንቶች ሮሜ 8፥34 እና የሐዋ. 4፥12፣ እነዚህ ጥቅሶች አርዮሳውያን ሁሉ ቀድመው ከአፋቻው የሚያወጧቸው አብሪ ጥይቶቻቸው ነበሩ።

[103] (St. Athanasius, *ad Serap.*, T. 28).

እንሥቶ ከአባቶች ወደ አባቶች እየተላለፈ የመጣውና በቤተ ክርስቲያን የተጠበቀው የክርስትና እምነት መሠረታዊው እምብርትና አስኳል ነው። በቀደሙት ዘመናት በግኖስቲኮች፣ በአርዮሳውያንና በመሰል መናፍቃን፣ ኋላም በእነ ማርቲን ሉተርና የፕሮቴስታንት ቡድኖች የደረሰው እንዳይርስበት የሚፈልግ ሰው ሁሉ መጽሐፍ ቅዱስን ሊያነብና ሊተረጉም የሚገባው በዚህ የእምነት እይታ ሊሆን ይገባዋል።

ቅዱስ አትናቴዎስ የአርዮሳውያንን ክርክሮችና ለማስረጃነት የሚጠቅሷቸውን ጥቅሶች ሲመረምር፣ በእነርሱ የተጠቀሱትን ጥቅሶች ወደ መመርመር የሚገባው፣ በመጀመሪያ ጥቅሶቹን ወደ ትክክለኛው እይታና ቦታ ከመለሳቸውና የክርስትናን እምነት መሠረታዊ ጭብጥ ጠቅለል አድርጎ ከገለጠና ካስቀመጠ በኋላ ነበር።በአንጻሩ የአርዮሳውያን አጠቃቀስ ግን እንደ ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች አጠቃቀስ በራሳቸው መንገድ ብቻ የሚሄድ እንጂ ከቤተ ክርስቲያን ነጽሮተ እምነት ጋር የሚሄድ አልነበረም።

**ቅዱስ ባስልዮስ ታላቁ - "ያልተጻፉ ይትበሃሎች"**

መጽሐፍ ቅዱስን ራሳቸው ለመሰላቸው አረዳድና ለፈጠሩት እምነት ማስረጃ እንደሆነ እያስመሰሉ በመጥቀስ አርዮሳውያኑ እነ ዩኖሚየስ የፈጠሩትን የጥቅስ ለጥቅስ ሽኩቻ ለመስበር፣ ቅዱስ ባስልዮስ በቤተ ክርስቲያን ያሉትን "ያልተጻፉ ይትበሃሎች" የእምነቷ መግለጫዎችና ማስረጃዎች መሆናቸውን በአጽንኦት አስረድቷል። የጽንፈኛው አርዮሳዊ የዩኖሚየስና መሰሎቹ ዋናው ችግራቸው መጽሐፍ ቅዱስን ከእነዚህ ቤተ ክርስቲያን እምነቷን በውስጣቸው ከያዙና ከምትጠብቅባቸው ያልተጻፉ ይትበሃሎች ወጥተው በራሳቸው ስሜት መንጎዳቸው መሆኑን አስረድቷል። እነዚህ ያልተጻፉ ይትበሃሎች የሚጠበቁትና የሚተላለፉት በ "ምስጢራት አማካይነት" ነው ይላል። ይህም ማለት በሥርዐተ አምልኳዊ ክዋኔዎችና ሕይወታዊ መንገዶች ያሉና የሚተላለፉ ናቸው።

ቅዱስ ባስልዮስ እነዚህ ምን ማለት እንደሆኑ ለማስረዳት የተለያዩ ምሳሌዎችን ጠቅሷል። ለምሳሌ በጥምቀት ጊዜ የሚደረጉ ነገሮች - ተጠማቂው ፊቱን ወደ ምዕራብ አዙሮ ዲያብሎስን እንዲክድ መደረጉ፣ ቀጥሎ ወደ ምሥራቅ ዞሮ በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ አምናለሁ ማለቱ፣ በመጠቂያው ውኃ ሦስት ጊዜ ብቅ ጥልቅ መደረጉ፣ . . . እነዚህ በውስጣቸው የቤተ ክርስቲያንን እምነት የያዙና የሚጠብቁ፣ እንዲሁም መግባቢያ መንገዶችም ናቸው ሲል ያስረዳል። እነዚህ ምልክቶችና ሥርዓቶች በመጽሐፍ ቅዱስ ላይ የተጻፉ አይደሉም፣ ሆኖም የቤተ ክርስቲያን እምነትና ሥርዐተ አምልኮመፈጸሚያና መጠበቂያ ክዋኔዎች ግን

ናቸው። ተግባራቸውም ለተጠማቂዎች "የእምነትን መርሕ" እንዲረዱ ማድረግና ከዚያ ቀጥሎም እንዲጠመቁ ማዘጋጀት ነው።

ቅዱስ ባስልዮስ እነዚህን ያልተጻፉ ይትበሃሎች ምስክርነት መጥቀሱ የቤተ ክርስቲያንን ሕያው እምነት ምስክር ከማድረግ ውጭ ሌላ ነገር አይደለም። ጥቅሶችን በደረቅ ሎጂክ ብቻ እንተረጉማለን የሚሉት ሐሳበ ግትሮቹ አርዮሳውያን ፈጥረውት የነበረውን ንትርክ መስበር ስለነበረበት ነው። መጽሐፍ ቅዱስን መረዳት የሚቻለው በቤተ ክርስቲያን በተግባራዊ ሕይወትና ክዋኔ ያሉትን ያልተጻፉ ይትበሃሎች በማየትና በመረዳት ነው እንጂ ጥቅስ ከጥቅሰ እያጋጩ በአሪስቶትል የሎጂክ ስልት ለመተርጎም በመሞከር አይደለም። ስለዚህም ቅዱስ ባስልዮስ በምስጢራት ክዋኔዎችና ሥርዐተ አምልኳዊ ይትበሃሎች ከሚገለጸውና "ያልተጻፈ" ከሆነው ከዚህ የቤተ ክርስቲያን "የእምነት መርሕ" ውጭ የመጽሐፍ ቅዱስን እውነተኛውን ሐሳብ ለመረዳት የማይቻል መሆኑን በአጽንኦት አስረድቷል።

በአራተኛው መቶ ዓመትና ከዚያም በኋላ የነበሩት የቤተ ክርስቲያን አባቶች አጠቃላይ አቋም ይህ ነበር። ይህም ከእነርሱ በፊት ከተነሡት አባቶች አስተምህሮና አቋም ጋር አንድ ነው። ቅዱስ ጄሮም ይኸን የአባቶችን መሠረታዊ አቋም ጠቅለል አድርጎ እንዲህ ገልጾታል፡-

> መርቅያንና ባሲሊድስ፣ እና ሌሎችም መናፍቃን ሁሉ ... የእግዚአብሔርን ወንጌል ገንዘብ አላደረጉም። . . . ወንጌል ማለት ትርጉሙ (ሐሳቡ፣ መልእክቱ) ነው እንጂ ገጸ ንባቡ ነው ብለን አናስብም፤ በውጫዊ ቆዳው ሳይሆን በውሳጣዊ ይዘቱ፣ በስብከት ቅጠሎቹ ላይ ሳይሆን በትርጉም ሥሩ ነው እንጂ። በዚህ ሁኔታ መጽሐፍ ቅዱስ ለሚያነቡትና ለሚሰሙት በእውነት የሚጠቅማቸው የሚሆነው ያለ ክርስቶስ የማይነገር ሲሆን ነው፣ ከአባቶች አስተምህሮና አረዳድ ሳይለይ የቀረበ ሲሆን ነው፤ የሚሰብኩት ሰዎች ያለ መንፈስ ቅዱስ የማይናገሩ ሲሆኑ ነው። . . . የክርስቶስን ወንጌል በተጣመመ አተረጓጎም የሰዎች ወንጌል እንዳናደርገው በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ያለ ጥንቃቄ መናገር ታላቅ አደጋ አለው።[108]

እስካሁን እንደ ተመለከትነው የእግዚአብሔርን ቃል በትክክል የመረዳት ጉዳይ በቅዱስ ሄሬኔዎስ ዘመን፣ በቅዱስ አትናቴዎስ ዘመን፣ በቅዱስ ባስልዮስ ዘመን፣ ዋና መሠረታዊ ጉዳይ ነበር። ይህ የሆነውም መጽሐፍ ቅዱስን እየጠቀሱ ወደ ስሁት የገቡ የተለያዩ መናፍቃን በመፈጠራቸው ነበር። በመጽሐፍ ቅዱስ የተጻፈውን

[108] in Galat., I, 1, II; M. L. XXVI, c. 386).

የእግዚአብሔር ቃል በትክክል ለመረዳትና ወደ ኑፋቄ ሳይሆን ወደ እውነት ለመድረስ መጽሐፉን ማንበብ ብቻውን በቂ ስላልሆነ "በእምነት እይታ"፣ "በመርሐ እምነት" ልናየውና ልንረዳው እንደሚገባ እነዚህ አባቶች ደጋግመው አስተምረዋል።

ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን መጽሐፍ ቅዱስን የቅዱስ ትውፊት ምልዐታዊ አካል አድርጋ ስለምትረዳውና ስለምትይዘው ይህ አረዳድ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ከሚሉት ፕሮቴስታንቶች ይልቅ መጽሐፍ ቅዱስን በእውነትና በተጻፈበት ዓላማ ለመጠበቅ የምትችለው እርሷ ናት። ምክንያቱም በኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ማንም ሰው ተነሥቶ የራሱን ግምትና ስሜት በመጽሐፍ ቅዱስ ስም ማስተማር አይችልም፤ መቆጣጠሪያና መለኪያ መርሐ እምነት አላትና። በአንጻሩ በፕሮቴስታንቶች ዘንድ ግን እንኳንስ ቅዱሱ የእግዚአብሔር ቃል የሆነው መጽሐፍ ቅዱስ ሊያስተምረውና ሊደግፈው ቀርቶ በጽኑ የሚቃወመው ነገር ሁሉ በስሙ እየተነገረና እየተደረገ ነው። ፕሮቴስታንቲዝም በባሕርዩ ይህን መቃወምና መከላከል አይችልም፤ ምክንያቱም ደጋግመን ለማየት እንደ ሞከርነው አንደኛው "እኔ የተረዳሁት እንደዚህ ነው" ብሎ ቢነሣ፣ ሌላኛው "ትክክል አይደለህም" ብሎ ለመቃወም ዐቅም አይኖረውም፤ ከመጀመሪያው ግላዊ አረዳድ የተፈቀደ ነውና። ስለዚህ ቅዱስ ትውፊት መጽሐፍ ቅዱስን ከተሳሳተ አነባበብና አረዳድ የሚጠብቀው፣ እንዲሁም ትክክለኛውን መጽሐፍ ቅዱሳዊ አስተምህሮ በእርግጠኛነት የሚያስረዳና እውነተኛውን አስተምህሮ ከስህተቱ ለይቶ ፍንትው አድርጎ የሚያሳይ መስተዋት ነው።

## 1.14 ፕሮቴስታንቶች በትውፊት ላይ የሚያነሷቸው ጥያቄዎችና ተቃውሞዎች

ከዚህ ቀጥሎ ፕሮቴስታንቶችና መሰሎቻቸው በትውፊት ላይ የሚያነሷቸውን ጥያቄችና ተቃውሞዎች እንመልከት።

1. "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን አስተምህሮ የማይቀበሉ ኦርቶዶክሶችና ሌሎችም አካላት፣ መጽሐፍ ቅዱስ ሙሉ መሆኑንና በመንፈስ ቅዱስ የተቃኘና ከስህተት የጸዳ እውነተኛ የእግዚአብሔር ቃል መሆኑን አይቀበሉም። ትውፊት ያስፈልጋል የሚሉት ስለዚህ ነው።"

ይህ ጉዳይ እኛ በማንለው መክሰስ (straw man) እንጂ እውነትነት የለውም። ምክንያቱም እኛ ኦርቶዶክሳውያን መጽሐፍ ቅዱስን እውነተኛ የእግዚአብሔርን ቃል የያዙ በመንፈስ ቅዱስ የተቃኙ መሆናቸውን እናምናለንና። ስለምናምነው

የምናውቀውና ልንመሰክር የምንችለው እኛ እንጂ ሌላ ሊሆን አይችልም። እነርሱንም ስህተታቸውን የምናሳያቸው በአዋጅ በሚያምኑት መሠረት እንጂ እነርሱ የማያምኑትን በሐሰት "እንደዚህ ያምናሉ" እያልን አይደለምና። ትውፊት የነበረውና ያለው፣ የሚያስፈልገውም መጽሐፍ ቅዱስ በቂ ስላልሆነ አይደለም፣ ከስህተት የጸዳና በመንፈስ ቅዱስ የተቃኘ መሆኑን ካለመቀበልም አይደለም። ትውፊት የነበረውና የሚያስፈልገው የመጽሐፍ ቅዱስን ትክክለኛ ሐሳቡንና መልእክቱን ለመረዳትና በእነርሱ የደረሰው መጽሐፍ ቅዱስን የግለሰቦች መጫወቻ የማድረግ አደጋ ላይ ላለመውደቅ ነው።

2. "ሐዋርያት በቃል ስላስተማሯቸውና ሊጠብቋቸው ስለሚገባቸው ትውፊቶች በተመለከተ የተናገሯቸው ነገሮች የግድ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ያሉ ነገሮች መሆናቸውን አያመለክትም። በቃላቸው ያስተማሯቸው ትምህርትም በመልእክቶቻቸው የጻፉላቸውን እነዚያኑ ትምህርቶች የመሆን እድሉ በጣም ጠንካራ ነው።"

እኛም ቅዱሳን ሐዋርያት በቃላቸው ያስተማሩትና ይጠበቅ ዘንድ ያዘዙት ትውፊት ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ ሌላ ነገር ነው አላልንም። በቃል የተሰበከና ያልተጻፈም ሆነ በመልእክታቸው የተጻፈ፣ ሁለቱም አንድ ወንጌል እንጂ የተለያየ ወንጌል አይደለም። ልዩነቱ ወንጌል መሆኑ ላይ ሳይሆን የተላለፈበት መንገድ ነው፤ አንዱ በጽሑፍ ሲሆን ሌላኛው ደግሞ በቃል ትውፊት መሆኑ ነው። ስለዚህ ትውፊትን ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ እንደሆነና ሌላ ሁለተኛ ነገር እንደሆነ አስመስሎ ማቅረብ ማሩን ማምረር ወተቱን ማጥቆር ካልሆነ በስተቀር ተገቢ አቀራረብ አይደለም።

ከዚህም ጋር "በቃላቸው ያስተማሯቸው ትምህርትም በመልእክቶቻቸው የጻፉላቸውን እነዚያኑ ትምህርቶች የመሆን እድሉ በጣም ጠንካራ ነው" የሚለው ጥያቄያዊ ሐሳባቸው ማረጋገጫው ምንድን ነው? በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በግልጽ እንደዚህ የሚል ወይም ይህን የሚያመለክት ፍንጭ የለም። ለምሳሌም ቅዱስ ጳውሎስ "የቀረውን ነገር በመጣሁ ጊዜ እደነግጋለሁ" አለ እንጂ "በሌላው መልእክቴ ላይ እጽፍላችኋለሁ ወይም ጽፌላችኋለሁ" አላለም። ወይም ደግሞ "የቀረውን ነገር በመጣሁ ጊዜ እደነግጋለሁ" ያለውን ነገር "እንደዚህ ባለው መልእክቴ ላይ ጽፌላችኋለሁ" አላለም። ስለዚህ ይህ ሐሳብ "እንዲህ ቢሆንልኝ እመኛለሁ" የሚል ምኞታዊ ሐሳብ ወይም ግምት እንጂ ምንም ጭብጥም ሆነ ማስረጃ የለውም። እንዲያው ትውፊትን ከመጥላታቸው የተነሣ "በቃላቸው ያስተማሯቸው ትምህርትም በመልእክቶቻቸው የጻፉላቸውን እነዚያኑ ትምህርቶች የመሆን እድሉ በጣም ጠንካራ ነው" ይላሉ እንጂ ይህ ጠንካራ የመሆን ዕድል የሚሉት ነገር ጠንካራነቱ ለእነርሱ ብቻ የሆነ ምኞት ነው።

፫. "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ የሚለውን የሚቃወሙና ትውፊት ያስፈልጋል የሚሉ ብዙዎች፣ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ (ያልተጻፈ) የእምነት መመሪያ የሆነ ምሳሌ ማቅረብ አይችሉም።"

በእርግጥ ብዙ ምሳሌዎችን ማቅረብ እንችላለን እንጂ! ለምሳሌም፦

- መጽሐፍ ቅዱስ የእግዚአብሔር ቃል መሆኑ የተገኘው ከትውፊት ነው። መጽሐፍ ቅዱስን የተቀበልነው ራሱ 'ቅዱስ መጽሐፍ ነኝና እመኑብኝ' ስላለ አይደለም። 'ከሰማይ ተጠቅልዬ የወረድኩ ቅዱስ መጽሐፍ ነኝ' የሚሉትን ሳንቀበል መጽሐፍ ቅዱስን ግን የተቀበልነው ከቤተ ክርስቲያን የተቀበልነው (ትውፊት) ስለሆነ ብቻ ነው። ይህ ደግሞ መሠረታዊ የእምነት አስተምህሮ ነው። ስለዚህ ቅዱሳት መጻሕፍት የእግዚአብሔር ቃል መሆናቸውን ስናምን ትውፊትን እየተቀበልንና እያተገበርን ነው ማለት ነው።
- የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ቀኖና - ማለትም በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የተካተቱት መጻሕፍት ማንነትና ቁጥራቸው - ከትውፊት የተገኘ እንጂ ከራሱ ከመጽሐፍ ቅዱስ የተገኘ አለመሆኑን ከላይ ተመልክተናል። ራሱ መጽሐፍ ቅዱስ በቤተ ክርስቲያን የተመረጡት መጻሕፍት ስብስብ ነው እንጂ የትኞቹ መጻሕፍት ሊካተቱ እንደሚገባቸው እና ብዛታቸው ስንት ስለመሆኑ አይናገርምና።
- ወንጌል አራት ብቻ መሆኑ፣ እንደዚሁም እነዚህ አራት ወንጌሎች የተጻፉት በማቴዎስ፣ በማርቆስ፣ በሉቃስና በዮሐንስ መሆኑ ከትውፊት የተገኘ መሠረታዊ እውነት ነው።
- የክርስቲያኖች ሰንበት እሑድ መሆኗ - ይህም ከትውፊት የተገኘ እንጂ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በግልጽ የተጻፈ አይደለም።
- የሕፃናት ጥምቀት - ሁሉም የቤተ ክርስቲያን አባቶች ሕፃናት እንዲጠመቁ አስተምረዋል። መጽሐፍ ቅዱስ የትም ቦታ ላይ በግልጽ ሕፃናት ይጠመቁ ወይም አይጠመቁ አይልም። ባልጎላ ሁኔታ ሰወር ብሎ ሊኖር ይችላል እንጂ። ትውፊት ግን ይህን ግልጽና የማያሻማ ያደርገዋል።

ለምሳሌም ቅዱስ አቡሊዴስ እንዲህ ብሏል፦

➢ ሕፃናት ልጆችን መጀመሪያ ያጥምቋቸው። ሲጠመቁ በራሳቸው

መልስ መስጠት ከቻሉ ይመልሱ። ካልቻሉ ግን ወላጆቻቸው ወይም ከቤተሰቡ መካከል አንደኛው መልስ ይስጥላቸው። ከዚያ ቀጥሎ ደግሞ ትልልቅ ወንዶችን ያጥምቁ፤ በመጨረሻም ሴቶችን ያጥምቁ።" (ቅዱስ አቡሊዲስ፣ ቀኖናት ዘሐዋርያት፣ 21፡3-5)

- ጸሎተ ቅዳሴ -ቤተ ክርስቲያን የመዳን ምስጢራትን የምትፈጽምበትና እምነቷን በተግባር የምትኖርበት ጸጋ የሆነው ጸሎተ ቅዳሴ ከትውፊት የተገኘ ነው። የፕሮቴስታንት ወገኖቻችን ነገረ እግዚአብሔር መላ ቅጡ ጥፍት ያለው የሆነው ራሳቸውን ከዚህ ትውፊት ውጭ በማድረጋቸው ነው።

- ወደ ምሥራቅ ዞሮ መጸለይ
- በመስቀል ምልክት ማማተብ
- በጥምቀት ጊዜ ተጠማቂው በመጠመቂያው ውኃ ሦስት ጊዜ ገብቶ መውጣት . . .

በክርስትና ውስጥ ይህን የመሰሉ ከሐዋርያዊ ትውፊት የተገኙ ብዙ ነገሮች አሉ። ከእነዚህ ሁሉ በተለይ ቀዳሚው ምሳሌ የጸሎተ አኰቴት አፈጻጸምን በተመለከተ ያለው (ሥርዓተ ቅዳሴ) ነው። ለምሳሌም ሰማዕቱ ቅዱስ ዮስጢኖስ በዘመኑ የነበረውን የጸሎተ ቅዳሴ ሂደት በተመለከተ እንዲህ ብሎ ጽፎ እናገኘዋለን፡-

> እሑድ በምንለው ቀን በከተማውም ሆነ በገጠሩ የሚኖሩ ሁሉም ክርስቲያኖች በአንድ ቦታ በኅብረት ይሰበሰባሉ። ሐዋርያት የጻፏቸው ወንጌሎችና መልእክቶች፣ እንዲሁም የነቢያት መጻሕፍት ጊዜው የፈቀደውን ያህል ይነበባሉ። አንባቢው አንብቦ ሲጨርስ፣ ሥርዓተ አምልኮውን የሚመራው በዚያ ለተሰበሰቡት ክርስቲያኖች በምንባቡ ውስጥ የሰሟቸውን ውብ ነገሮች አርአያ ያደርጓቸው ዘንድ ትምህርትና ተግሣጽ ይሰጣቸዋል። ከዚያም ሁላችንም በኅብረት አንድ ላይ እንነሣና ስለ ራሳችንና በየትም ቦታ ቢሆን ስለ ሌሎችም ሁሉ ጸሎት እናደርሳለን፤ በሕይወታችንና በድርጊቶቻችን ሁሉ እውነተኞች በመሆን ለትእዛዛቱም ታማኞች እንሆን ዘንድና በዚህም ዘለዓለማዊ ድኅነትን እናገኝ ዘንድ።
>
> ጸሎቶቹ ሲያልቁ እርስ በእርሳችን ሰላምታ እንሰጣጣለን (እንሳሳማለን)። ከዚያም ኅብስትና ውኃ የተቀላቀለበት ወይን በጽዋ አድርጎ ለካህኑ ይቀርብለታል። ካህኑም እነዚያን ተቀብሎ እኛን ይህን ጸጋ ለመቀበል የበቃን ስላደረገን ረዘም ላለ ጊዜ ለዓለማት ፈጣሪ ለአብ ለወልድ ለመንፈስ ቅዱስ ክብርና ምስጋና (በግሪክ - ዩካሪስቲያ) ያቀርባል። ጸሎቱንና

ምስጋናውን ሲጨርስ በዚያ ያሉት ሁሉም "አሜን" በማለት ከምስጋናውና ከጸሎቱ ሱታፌያቸውንና ኅብረታቸውን ይገልጻሉ። ካህኑ ጸሎተ አኰቴቱን ሲጨርስና ሕዝቡም አሜን ብለው ተሰጥኦውን ከመለሱ በኋላ ዲያቆናት ብለን የምንጠራቸው እነርሱ ካህኑን በመራዳት ለምእመናኑ ሥጋውንና ደሙን ያቀብላሉ። (Apology 1, 65-67)

በሐዲስ ኪዳን ካሉት መጻሕፍት ውስጥ በአንዳቸውም ውስጥ የክርስቲያኖች አምልኳቸው እንዴት እንደ ነበረ በዝርዝር የተጻፈ ነገር አናገኝም። ግን ሥርዐተ አምልኮ አልነበራቸውም ማለት አይደለም። ይህ ማለት ያ የነበራቸው ሥርዓተ አምልኮ እንዴት እንደ ነበረ በቀደሙት የቤተ ክርስቲያን አባቶች ጽሑፎችና ትምህርቶች እናገኘዋለን። ከዚያም በላይ ሕይወቱ በተግባር ሲተላለፍልን የመጣ ስለሆነ በቅድስት ቤተ ክርስቲያን ውስጥ በተግባር እናገኘዋለን። የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ግን የተጻፉበት ዓላማ ሥርዓተ አምልኮን በዝርዝር ለመግለጽ ስላልነበረ ይህን በዝርዝር አልጻፉልንም። ከሐዋርያዊ ትውፊት ውጭ ያሉ ፕሮቴስታንቶች በየሳምንቱ እነርሱ ደስ ባላቸው መንገድ እናመልካለን እያሉ ዛሬ ከደረሱበት ቅጥና መልክ ያጣ "አምልኮ" ላይ ደርሰዋል። ይህም ሐዋርያዊውን ቅዱስ ትውፊት ስላልተቀበሉ ነው።

እስኪ ተሐድሶ ፕሮቴስታንቶች የሚከተሉትን ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የት እንደሚገኙ ሊያስረዱን ይችላሉን?

1) የመጽሐፍ ቅዱስን መጻሕፍት ብዛት ወይም ቁጥር እነርሱ እንደሚሉት 66 ናቸው የሚል ጥቅስ፤

2) "ሥላሴ" የሚል የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ፤

3) የክርስቲያኖች ሰንበት እሑድ ነው የሚል የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ፤

እነዚህን በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በቀጥታ ያልተጻፉ ትምህርቶችን የሚቀበል ማንኛውም ፕሮቴስታንት ትውፊትን መቀበሉ ነው፤ ይህም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን መሠረታዊ እምነቱን አፍርሷል ማለት ነው።

ከዚህም በላይ ሐዋርያዊ የሆነውን ሥርዓተ ቅዳሴ አለማወቃቸውና ከዚያ ሐዋርያዊ ትውፊት መለየታቸው ስለ ቅዱስ ቁርባን ያለውን ትክክለኛ አረዳድና እምነት ከማወቅና ከማመን ውጭ አድርጓቸዋል። በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን ከሐዋርያት ጀምሮ በነበረው ሥርዓተ አምልኮ ቅዱስ ቁርባን ምን ተብሎ እንደሚታመንና እንዴት እንደሚፈጸም ያለውን እምነትና ትምህርት ትተው በራሳቸው ሙከራ

ለመረዳት እንደ አዲስ "ሀ" ብለው በመጀመራቸው ታላቁንና ገናናውን ምስጢረ ቁርባንን በተመለከተ ያላቸው እምነትና ትምህርት ሐዋርያትና የቀደሙ የቤተ ክርስቲያን አባቶች ካመኑትና ካስተማሩት ተቃራኒ የሆነ እንግዳ እምነትና ትምህርት ሆኖባቸዋል።

ስለዚህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለውን የሚቃወሙና ትውፊት ያስፈልጋል የሚሉ ሰዎች ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ (ያልተጻፈ) የእምነት መመሪያ የሆነ ምሳሌ ማቅረብ አይችሉም" የሚለው ሐሳባቸው በዚህ ሁሉ እውነት ፊት መቆም የማይችል ነው።

4. "መጽሐፍ ቅዱስ መዳንን በተመለከተ ግልጽ ነው። ይህ ግልጽ የሆነው አስተምህሮ የማይገባቸው ካሉ ችግሩ የራሳቸው እንጂ የመጽሐፍ ቅዱስ አይደለም፤ አለበለዚያ "ነገር ግን ኢየሱስ እርሱ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደ ሆነ ታምኑ ዘንድ፣ አምናችሁም በስሙ ሕይወት ይሆንላችሁ ዘንድ ይህ ተጽፏል" (ዮሐ. 20፡31) የተባለው ቃል ታበለ ማለት ነው?"

እንደዚያ ከሆነ (መጽሐፍ ቅዱስ መዳንን በተመለከተ ለማንም ሰው ግልጽ ከሆነ)፣ ሉተራኖች፣ ሪፎርምድ ፕሮቴስታንቶች፣ ሜቶዲስቶች፣ ካሪዝማቲኮች፣ መጥምቃውያን፣ ጴንጤ ቆስጤዎች፣ እና ሌሎቹም የፕሮቴስታንት ቡድኖች አንዳቸው ከሌላቸው ለምን ተለያዩ? የሚስማሙት "መዳን በእምነት ብቻ" በሚለው ብቻ እንጂ ከዚያ ውጭ ያ መዳን ምንድን ነው? አንዴ ያመነ ሰው መዳኑን ሊያጣ ይችላል አይችልም? ሰው የሚድነው በእግዚአብሔር ምርጫ ብቻ ነው ወይስ በራሱ ነጻ ፈቃድ በሚወስነው ውሳኔ? በመዳን ውስጥ ጥምቀትና ቁርባን ያላቸው ሚና ምንድን ነው? መልካም ሥራስ ድርሻው ምንድን ነው? . . . በእነዚህና በመሳሰሉት የመዳን ጉዳች ላይ አንዳቸው ከሌላቸው አይስማሙም። ስለዚህ ይህ ሐሰብ መነሻው ትክክል አይደለም።

5. "ሐዋርያው ጴጥሮስ 'በእነዚያ ዘንድ ለማስተዋል የሚያስቸግር ነገር አለ' አለ እንጂ (2 ጴጥ. 3፡16) እነዚህ ነገሮች ሊታወቁ የማይችሉ ናቸው አላለም። ስለዚህ በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ሊታወቅ የማይችል ነገር ስለሌለ ትውፊት የሚባል ነገር አያስፈልግም።"

እኛ ኦርቶዶክሳውያንም መጽሐፍ ቅዱስ ሊታወቅ አይችልም አንልም። የምንለው ሐሳባቸው ጠንካራ የሆኑ የመጽሐፍ ቅዱስ አንቀጾች ራሱን መጽሐፍ ቅዱስን በማንበብ ብቻ ወይም ጥቅስና ጥቅስ በማነጻጸርና በመሳሰሉት ፕሮቴስታንቶች ይረዳሉ በሚሏቸው ዘዴዎች ምስጢራቸው ተስተካክሎ ሊታወቁ አይችሉም ነው እንጂ ፈጽሞ ሊታወቁ አይችሉም አንልም። ለመረዳት ደግሞ በቤተ ክርስቲያን

መርሐ እምነትና አባቶቻችን የጻፏቸውን ትርጓሜያት መመልከት፣ በዘመኑ ያሉ አባቶችንም መጠየቅ ይገባል ነው የምንለው እንጂ ፈጽሞ የማይታወቁ ናቸው አላልንም። ትውፊት የሚያስፈልገውም በፕሮቴስታንት ወገኖቻችን እንጂ ያረሰው በየጥቅሱ እየተነታረኩ በመለያየት በየቀኑ አዳዲስ ቸርች ከመክፈትና ለሕይወት በተሰጠው የሕይወት ቃል ሞትን ላለመሸመት ነው። ስለዚህ ይህ የመከራከሪያ ነጥባቸው መሠረተ ሐሳቡ ስህተት ስለሆነ ከቁም ነገር ገብቶ ሊቆጠር አልቻለም።

6. "ዮሐንስ 'ብርሃንም በጨለማ ይበራል፣ ጨለማም አላሸነፈውም' ብሏል። ዮሐ. 1፡8 ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስን አንብበው ወደ እውነት የማይደርሱ ካሉ ችግሩ በጨለማ ውስጥ ያሉ ሰዎች ብርሃንን ማየት ስለማይችሉ ብቻ ነው።" [109]

ነገሩ እነርሱ እንደሚሉት እንደዚህ ከሆነ፣ ማለትም "መጽሐፍ ቅዱስን አንብበው ወደ እውነት የማይደርሱ ካሉ ችግሩ በጨለማ ውስጥ ያሉ ሰዎች ብርሃንን ማየት ስለማይችሉ ብቻ ነው" እንዳሉት ከሆነ፣ ከሉተርና ከዝዊንግሊ መካከል ብርሃንን ማየት ያልቻለው ማንኛው ነበር? ከሉተርና ከካልቪን መካከልስ በጨለማ ውስጥ የነበረው ማንኛው ነበር? በምስጢረ ጥምቀት ላይ፣ በምስጢረ ቁርባን ላይ፣ በመዳን ላይ፣ እና በመሰሉት መሠረታዊ ጉዳዮች ላይ ከማይስማሙትና 40,000 ከሆኑት ዲኖሚኒሽኖች ውስጥ ብርሃኑን ማየት ያቃታቸው የትኞቹ ናቸው? ይህን መበየን የሚችለውስ ማን ነው? በምን መስፈርት?

በዚያውም ላይ ብርሃንን ማየት የሚችል የሆነ ሰው መጽሐፍ ቅዱስን በግሉ በማንበብ ብቻ ትክክለኛውን የመጽሐፍ ቅዱስ አስተምህሮ ማወቅ የሚችል ከሆነና ይህ ደግሞ ፕሮቴስታንቶቹ እነርሱ እናምነዋለን የሚሉት ነገር ከሆነ፣ ከቀደምት የቤተ ክርስቲያን አባቶች መካከል ከእነርሱ ጋር ሙሉ በሙሉ የሚስማማ አስተምህሮ የነበረውና ቤተ ክርስቲያን የምትቀበለው አንድ አባት እንኳ እስኪ ይጥሩልን! እንደዚያ ቢሆን ኖሮ የቅዱሳን ሐዋርያት ደቀ መዛሙርት ከነበሩት፣ ከእነርሱ ቀጥሎ ከተነሡት፣ የቤተ ክርስቲያን አስተምህሮና የመዳን ጸጋ ለመጠበቅ ከግኖስቲኮችና ከአርዮሳውያን ጋር ጽኑ ተጋድሎ ካደረጉት የቤተ ክርስቲያን ጠበቆችና ከሰማዕታት መካከል ፕሮቴስታንቶች እንደሚሉት ዓይነት እምነትና አስተምህሮ የነበረው እስኪ ማን ነበር? ማንም! ታዲያ የዛሬዎቹ ፕሮቴስታንቶች የሚያምኑትን አስተምህሮ የማይቀበሉ የነበሩት እነዚያ አባቶች ብርሃንን ማየት አይችሉም ነበርን? ስለዚህ መጽሐፍ ቅዱስን አንብቦ ሐሳቡን በሚገባ መረዳት አለመቻል የሚመጣው የግድ በጨለማ ከመሆን ወይም አለመሆን ሳይሆን በቤተ ክርስቲያን መርሐ እምነት መሠረት ካለማንበብና ካለመማር ነው።

[109] E. Gordon Rupp, trans, 1969, *Luther and Erasmus: Free Will and Salvation.*

7. “ትውፊትን ጌታ በማቴ. 15፡1-9 ፤ በማር. 7፡3፤5፤ 8 ላይ፣ ጳውሎስ ደግሞ በቆላ. 2፡8 ላይ ነቅፈውታል። ስለዚህ እነርሱ የነቀፉትን መቀበል ይገባል ወይ?

ትውፊት የሚለው ቃል (በግሪክ ፓራዶሲስ) በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ሐዋርያዊ ትምህርትን በተመለከተም (1 ቆሮ. 11፡2፤ 2 ተሰ. 2፡15)፣ እንዲሁም ደግሞ የፈሪሳውያንን የሐሰት ትምህርት በተመለከተም (ማር. 7፡3፤ 5፤ 8) ጥቅም ላይ የዋለ ቃል ነው። ጌታችን ፈሪሳውያንን የሰውን ወግ በመጠበቅ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ እያስረሱ መሆናቸውን በጽኑ ተግሣጽ ነግሯቸዋል። እዚህ ላይ “የፈሪሳውያን ወግ፣ የሽማግሎች ወግ” የተባለው ፈሪሳውያን በእግዚአብሔር ሕግ ላይ የጨመሩት ከሕጉ ጋር የማይሄድ፣ ይልቁንም ሕጉን የሚያፈርስ የሆነውን የራሳቸውን የፈጠራ ወግ ነበር። ጌታችን እንዲህ ብሎ እንዲናገር ያደረገው፣ ፈሪሳውያን “ደቀ መዛሙርትህ ስለ ምን የሽማግሎችን ወግ ይተላለፋሉ? እንጀራ ሲበሉ እጃቸውን አይታጠቡምና” ብለው የጠየቁት ጥያቄ ነበር። ለዚህ ሲመልስላቸውም እንዲህ አለ፡-

> እናንተስ ስለ ወጋችሁ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ስለ ምን ትተላለፋላችሁ? እግዚአብሔር፣ አባትህና እናትህን አክብር፤ ደግሞ፣ አባቱን ወይም እናቱን የሰደበ ፈጽሞ ይሙት ብሏልና፤ እናንተ ግን - አባቱን ወይም እናቱን፡- ከእኔ የምትጠቀምበት መባ ነው የሚል ሁሉ፣ አባቱን ወይም እናቱን አያከብርም ትላላችሁ፤ ስለ ወጋችሁም የእግዚአብሔርን ቃል ሻራችሁ። ማቴ. 15፡1-6

ከዐሥሩ ትእዛዛት መካከል አንደኛው “እናትህንና አባትህን አክብር” የሚለው መሆኑ ይታወቃል። አክብር ማለትም ሲደክሙ እርዳቸው ጡራቸው ማለትም ነው። ስለዚህም ልጆች ቤት ሲይዙ ወላጆቻቸውን የሚጦሩበት ገንዘብ ያጠራቅሙ ነበር። ፈሪሳውያን ግን ያን ልጆች ወላጆቻቸውን ለመርዳት የሚያጠራቅሙትን ገንዘብ ለመውሰድ ሲሉ አንድ ዘዴ ፈጠሩ። እርሱም አንድ ሰው ወላጆቹን ለመጦር ብሎ ያስቀመጠውን ገንዘብ ለቤተ መቅደስ ቢሰጥ ከዚያ በኋላ ወላጆቹን የመርዳትና የመንከባከብ ሐላፊነት አይኖርበትም የሚል የፈጠራ ትምህርት ማስተማር ጀመሩ።

ይህን ራሳቸው የፈጠሩትን ትምህርታቸውንም እንደ መልካም ነገር ከትውልድ ወደ ትውልድ ያስተላልፉት ነበር። ጌታችን “እናንተስ ስለ ወጋችሁ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ስለ ምን ትተላለፋላችሁ?” ያላቸው ለዚህ ነበር፣ ምክንያቱም እነርሱ በፈጠሩት የገንዘብ ማግኛ ትምህርት ምክንያት ሰዎች “እናትህንና አባትህን አክብር” የሚለውን የእግዚአብሔር ትእዛዝ እንዲተላለፉ እያደረጓቸው ነበርና። ጌታችን የገሠጻቸው ይህ ትውፊት (ወግ) ሰዎች ሕገ እግዚአብሔርን እንዲያፈርሱ የሚያደርግ በመሆኑ ነበር።

ታዲያ የፈሪሳውያንን ትውፊት ስህተት፣ የቤተ ክርስቲያንን ትውፊት ደግሞ ትክክል የሚያደርገው ምንድን ነው? አንደኛ የትውፊቱ ምንነት ሲሆን ሁለተኛ ደግሞ የትውፊቱ ምንጭ ነው። የፈሪሳውያን ትውፊት የእግዚአብሔርን ሕግ ወደ ማፍረስ የሚወስድ ነበር። ሐዋርያዊ የሆነው ክርስቲያናዊ ትውፊት ግን ሕገ እግዚአብሔርን የሚያስፈርስ ሳይሆን እንዲጸኑና እንዲጠበቁ የሚያደርግ ነው። የፈሪሳውያን ትውፊት ምንጩ በአስተምህሯቸውም ሆነ በተግባራዊ ሕይወታቸው ከእግዚአብሔር ርቀው የነበሩት ፈሪሳውያን ሲሆኑ፣ የቤተ ክርስቲያን ትውፊት ምንጭ ግን ከራሱ ከጌታችን የተገኘ ክርስቶሳዊ ነው።

ጌታችን የፈሪሳውያን ትውፊት ምንጩ ማን እንደሆነ ሲናገር "የሰዎች ወግ" ብሎ ገልጾታል። ማር. 7:8 በአንጻሩ የቤተ ክርስቲያንን ትውፊት በተመለከተ ደግሞ ቅዱስ ጳውሎስ "ወንድሞች ሆይ፣ በሁሉ ስለምታስቡኝና አሳልፌ እንደ ሰጠኋችሁ ትውፊትን (ወግን) (ፓራዶሲይስ - paradoseis) ፈጽማችሁ ስለ ያዛችሁ አመሰግናችኋለሁ" በማለት ገልጿል።[110] 1 ቆሮ. 11:2 ቅዱስ ጳውሎስ እነዚህን ትውፊቶች ከየት እንዳገኛቸው ስለ ምንጫቸው ሲናገር "ለእናንተ ደግሞ አሳልፌ የሰጠሁትን እኔ ከጌታ ተቀብያለሁና" በማለት ከጌታ የተቀበላቸው መሆኑን በግልጽ ጽፏል። 1 ቆሮ. 11:23 ኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ሐዋርያዊ ትውፊትን በተመለከተ ስትናገር ይህን ማለቷ ነው። ምንጩ ጌታችን ነው። ይህ እርሱ በቃሉ ትምህርትና በተግባሩ ያስተማራቸው ሁሉ ቢጻፍ ኖሮ "ሁሉ በእያንዳንዱ ቢጻፍ ለተጻፉት መጻሕፍት ዓለም ራሱ ባልበቃቸውም ይመስለኛል" እንደ ተባለው ነው። ዮሐ. 21:25 ቅዱሳን ሐዋርያት ይህን ከጌታ በምልዐት ያዩትንና የሰሙትን ሁሉ ለመላዋ ቤተ ክርስቲያን አቀበሏት፤ የዚህ ሀብት መዝገብ የሆነችው ቤተ ክርስቲያንም "የእውነት ዐምድና መሠረት" ሆነች። 1 ጢሞ. 3:15

---

110 መጽሐፍ ቅዱስን ከጥንት ቋንቋው ከዕብራይስጡ እና ከግሪኩ ወደ ሌላ ቋንቋ የሚተረጉሙ የፕሮቴስታንት ተርጓሚዎች የትርጉም ሥራቸውን ተጠቅመው የራሳቸውን እምነት በመጽሐፍ ቅዱሱ ቃል አስታክከው ሥርዋጽ ለማስገባት መሞከራቸው አልቀረም። ከእነዚህ የፕሮቴስታንት ትርጉሞች መካከል በተለይም ኒው ኢንተርናሽናል ቨርዥን (NIV) የተባለው ትርጉም ብዙ ነገሮችን በራሱ አስተምህሮ መሠረት ነው የተረጎመው። ከእነዚህ መካከልም:- በግሪኩ **ፕሪስባይተር** የሚለውን ቃል **ካህን** በማለት ፋንታ **ሽማግሌ** ብለው ተርጉመውታል። በግሪኩ **ፓራዶሲስ - ትውፊት** የሚለውን ቃል ሲተረጉሙ ደግሞ፣ ሐዋርያዊ ትውፊትን የሚገልጹበት ቦታ ላይ ፓራዶሲስን "ትምህርት - teaching (s)" ወይም "ትምህርቶች" ብለው የተረጎሟቸው ሲሆን፣ ሰው ሠራሽ የሆኑትንና የተነቀፉትን የሚገልጹበት ቦታ ሲሆን ደግሞ "ትውፊት - tradition" ብለው ተርጉመዋቸዋል። ከዚህም የተነሣ ይህን ነገር ሳያውቅ የNIV ትርጉምን የሚያነብ ሰው በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ያለው ብቸኛው ትውፊት ሰው ሠራሽ የሆነና ልንከተለው የማይገባ ሊመስለው ይችላል። እንደዚህ ያለው ሰው በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ሐዋርያዊ ትውፊት የሚባል ነገር ያለ ስለመሆኑ ምንም ላያውቅ ይችላል ማለት ነው። በእጃችን ላይ ባሉት በብዙዎቹ የአማርኛ የመጽሐፍ ቅዱስ ትርጉሞችም ላይም **ሐዋርያዊ ትውፊትን "ወግ"** ብለው ነው የተረጎሙት። የፕሮቴስታንት ሚሲዮናውያንና አገር በቀል ቅጥረኞቻቸው በቀላል አማርኛ ወይም ሌላ ቋንቋ ሽፋን መጽሐፍ ቅዱስ የእነርሱን የተሳሳተ አስተምህሮ እንዲደግፉቸው ለማድረግ በትርጉም ሽፋን ብዙ አሳዛኝ ወንጀሎችን ሠርተዋል፤ እየሠሩም ናቸው። ይህ አንድ ሰፊ ጥናት ይጠይቃል።

አንድ የሆነ ነገር አላግባብ ጥቅም ላይ ሊውል ይችላል ማለት በራሱ መጥፎ ነው ማለት አይደለም። ራሱን መጽሐፍ ቅዱስን እንውሰድ። በአግባቡ ለሚጠቀሙበት የሕይወት መንገድ ነው። በአግባቡ ለማይጠቀሙበት መናፍቃንና ከሃድያን ደግሞ ያንኑ መልካም የሆነውን መጽሐፍ ቅዱስን ለክህደታቸው ይጠቀሙበታል። ሆኖም ግን ይህን እንዲህ መሆኑን ስናይ መጽሐፍ ቅዱስ መጥፎ ነው ወይም አስፈላጊ አይደለም አንልም። ችግሩ የአጠቃቀሙ እንጂ የራሱ የመጽሐፍ ቅዱስ አይደለምና። ትውፊትም እንደዚሁ ነው። እንደ ፈሪሳውያን የራስን ስግብግብነት ለማስፈጸምና የራስን ነውር ለመሸፈን ታስቦ የሚፈጠር ከሆነ መጥፎ ነው። ሐዋርያዊ ምንጭ ያለውና ከቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ ጋር የሚስማማ ከሆነ ደግሞ መልካም ነው።

ስለሆነም እውነተኛ ትውፊት ከጌታ የተገኘና ሊቀበሉት የተገባ ነው። በአንጻሩ የፈሪሳውያን ትውፊት ደግሞ እነርሱ ራሳቸው የሰዎች ገንዘብ ለመቀማት ሲሉ የፈጠሩት የሐሰት ትምህርት ስለነበር ሊቀበሉት የማይገባ ነው። የፈሪሳውያን ትውፊት ስለተነቀፈ ትውፊት የሚባል ነገር ሁሉ ተነቅፏል ማለት ሰይጣን ከመጽሐፍ ቅዱስ ጠቅሶ ጌታን ስለ ፈተነው ከዚያ በኋላ ከመጽሐፍ ቅዱስ መጥቀስ ሰይጣንን መምሰል ነው እንደ ማለት ያለ ነው። መጽሐፍ ቅዱስን አላግባብ ጠቅሰው የሚያሳስቱ እንደ ሰይጣንና ግብረ አበሮቹ ያሉ እንዳሉ ሁሉ ለክርስትና እውነት ኀጂ የሆኑ ሰው ሠራሽ ትውፊቶችም (ወጎች) አሉ። ስለዚህ ጌታችንና ቅዱስ ጳውሎስ በአሉታ የጠቀሷቸው ትውፊቶች (ወጎች) ትውፊት የተባለው ሁሉ ትክክል ሊሆን እንደማይችልና ማጣራት እንደሚገባን ያስጠነቅቁናል እንጂ ትውፊት ሙሉ በሙሉ አያስፈልግም የሚሉ አይደሉም።

ስለዚህ ሐዋርያዊ ትውፊት ከሰው ሠራሽ ትውፊት ጋር ተደርቦ የተወቀሰ ሳይሆን እንቀበለውና እንጠብቀው ዘንድ የታዘዘ ስለሆነ ሰው ሠራሽ ከሆነው ትውፊት የተለየ ነው። መጽሐፍ ቅዱስ እንደ ፈሪሳውያን ያሉ የተሳሳቱ ትውፊቶችን እንደሚነቅፋቸው ሁሉ በአንጻሩ ደግሞ ሐዋርያዊ የሆኑትን ልንጠብቃቸው እንደሚገባ በአጽንኦት ይናገራል። ይህን ቀደም ብለን በቦታው ላይ ተመለክተነዋል። ስለዚህ ይህ የመከራከሪያ ነጥባቸው ስህተት ነው። እነዚህን ጥቅሶች ተደግፈው መጽሐፍ ቅዱስ የማይለውን የራሳቸውን የፈጠራ ትምህርት ለመጫን የሚደክሙት የፕሮቴስታንቶች ተቃውሞም ሆነ ጥያቄ መሠረት የለውም ማለት ነው።

8. "የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ከመጻፋቸው በፊት ትውፊት ቦታ ነበረው፤ ሆኖም የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ከተጻፉ በኋላ ግን ትውፊት ሙሉ በሙሉ በተጻፉት መጻሕፍት ተተክቷል፤ ስለዚህ ከዚያ ወዲህ ትውፊት ምንም ቦታ የለውም።"

"መጻሕፍቱ ገና እየተጻፉ ሳለ ትውፊት ቦታ ነበረው፣ ከተጻፉ በኋላ ግን ቦታ የለውም" የሚል መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ከየት ላይ ይገኛል? አንድም ቦታ ላይ እንዲህ የሚል የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል የለም። እንደዚሁም የሐዋርያት ትውፊት ሙሉ በሙሉ በጽሑፋቸው ላይ ብቻ የተገደበ ነው፣ ወይም ደግሞ ትውፊቱን በሙሉ በወንጌልና በመልእክቶቻቸው ላይ ጽፈውታል የሚልም የለም (2 ተሰ. 2፡15፤ 3፡6 ፤ 2 ጢሞ. 1፡13 ፤ 2፡2 ፤ 1 ቆሮ. 11፡2፤ 34)። ስለዚህ ይህ ሐሳብ ትውፊትን ከመጥላት የመጣ ምኞታዊ ሐሳብ ነው እንጂ ምንም ማስረጃ የለውም።

ቅዱስ ጳውሎስ በ2 ተሰ. 2፡15 ላይ "ወንድሞች ሆይ፣ . . . በቃላችንም ቢሆን . . . የተማራችሁትን ወግ ያዙ" በማለት ያዘዘው ትምህርቱ "በዚህ ዘመን አብቅቷል" የሚል መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ እንደዚህ የሚል አንድም ነገር የለም! የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ከተጻፉ በኋላ ትውፊትን ትታችሁ በተጻፈው ብቻ ተመሩ የሚል አንድም ጥቅስ የለም።

የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ከመጻፋቸው በፊትና በኋላ ትውፊት የነበረው ሚና የተለያየ ከሆነ፣ ለምሳሌ የማቴዎስ ወንጌል ሌሎቹ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ተጽፈው ባላለቁበት ዘመን ብቸኛው የእምነት መመሪያ ያልነበረ ከሆነ (ያን ጊዜ ትውፊትም አብሮ ነበር የሚለውን ይቀበላሉና)፣ ተጽፈው ሲያልቁ ግን በድንገት ብቸኛው የእምነት መመሪያ ሆነ (ትውፊት አበቃለት) ማለት በቤተ ክርስቲያን ታሪክ ውስጥ የሌለ ፈጠራ ነው። ይህ ማለት'ኮ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን የማቴዎስ ወንጌል የነበረው ቦታና ከዚያ በኋላ ባለችው ቤተ ክርስቲያን ያለው ቦታ የተለያየ ነው ማለት ነው! ሌሎች የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትም እንዲሁ በጥንቷ ቤተ ክርስቲያን የነበራቸው ቦታና ከዚያ ወዲህ ባለው ዘመን ያላቸው ቦታ ይለያያል እንደ ማለት ነው። ይህ ግን የፕሮቴስታንቶች ልብ ወለድ ሐሳብ ብቻ ነው። ስለዚህ ይህ ሐሳባቸው እንደ ሌሎቹ ሐሳቦቻቸው ሁሉ ምንም ጭብጥና ማስረጃ የሌለው ነው።

9. "ጳውሎስ በ2 ተሰ. 2፡15 ላይ ያዘዘው ነገር በዚሁ መልእክቱ ላይ የሆነ ቦታ፣ ወይም ደግሞ በሌሎቹ መልእክቶቹ የሆነ ቦታ ላይ የጻፈውን ማለቱ ሊሆን ይችላል እንጂ ያልተጻፈ ትምህርት አለና ያንን ያዙ ማለቱ ላይሆን ይችላል። ስለዚህ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ሌላ ትውፊት የሚባል ነገር የለም።"

በመጀመሪያ ይህ ግምት እንጂ የተረጋገጠ ነገር አይደለም። ቅዱስ ጳውሎስ በ2 ተሰ. 2፡15 ላይ ሲጽፍ፣ "ይህ ትምህርት ሌላ ቦታ ላይ የጻፍኩት ትምህርት ነው" አላለም! ስለዚህ ቅዱስ ጳውሎስ ያላለውን እንዳለ አስመስሎ ማቅረብ ስህተት ብቻ ሳይሆን ድፍረትም ነው። ከዚህ ባሻገር ደግሞ ቅዱስ ጳውሎስ በ2 ጢሞ. 2፡2 ላይ በግልጽ "ብዙ ሰዎች የመሰከሩለትን፣ ከእኔም **የሰማኸውን** ሌሎችን ደግሞ ሊያስተምሩ ለሚችሉ ለታመኑ ሰዎች አደራ

. . . የብሉይ ኪዳንና የሐዲስ ኪዳን አምላካዊ መጻሕፍት፣ እና የቃል ትውፊት ወይም ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ከሐዋርያት የተቀበለችው ሕያው እምነት - እነዚህ ሁለቱ በአንድነት አንድ የእምነት ምንጭ የሆነና አንድ መርሐ እምነትን ያስገኙ ናቸው። ሁለቱም የአንድ ነገር - እግዚአብሔር ሰውን ለማዳን በክርስቶስ ያደረገውን መገለጥ - ለመግለጥና ለመጠበቅ የሚያገለግሉ መሳሪያዎች ናቸው። ተግባራዊ ልዩነታቸው ይህ ነው፤ እርሱም የቤተ ክርስቲያን ትውፊት የቅዱሳት መጻሕፍቱን ቀኖና ይወስናል፤ የቅዱሳት መጻሕፍቱን ትክክለኛ ትርጓሜ ለመረዳት ቁልፉን ይሰጣል፤ ከኑፋቄያዊ አጠቃቀምም ዘበኛ ሆኖ ይጠብቃቸዋል።[111]

እንደዚሁም በተመሳሳይ በሊቅነቱ የሚታወቀው፣ በእምነቱ አንግሊካን ፕሮቴስታንት የሆነው ጄ. ኤን. ዲ. ኬሊ (J. N. D. Kelly) እንዲህ ብሏል፦

በመላው የክርስትና ዘመን ሁሉ መጽሐፍ ቅዱስ እና ትውፊት እርስ በእርስ ተመጋጋቢዎችና እንደ አንድ ምንጭ ተጠቃሾች ሆነው ሲያገለግሉ ኖረዋል። እነዚህም በይዘት አቀራረብ ቅርጻቸው የተለያዩ ቢሆኑም በይዘታቸው ግን አንድ ናቸው። የትኛው የበለጠ ሥልጣን ወይም የመጨረሻ የበላይ ነው? በሚል መንገድ መጠየቅ ጉዳዩን አሳሳችና ተገቢ ባልሆነ መንገድ ማቅረብ ነው። መጽሐፍ ቅዱስ በመርሕ ደረጃ በቂ ከሆነ፣ ትውፊት ደግሞ ለመጽሐፍ ቅዱስ ትርጓሜ አስተማማኙና ትክክለኛው መንገድና መሪ ተደርጎ ይወሰድ ነበር። ቤተ ክርስቲያን ቅዱሳት መጻሕፍትና ትውፊት በአንድነትና በስምምነት የሚመሰክሩለትን የእግዚአብሔር መገለጥ እውነተኛ ዓላማና ትርጉም ትክክለኛውን ጭብጥ ከሐዋርያት የተቀበለችውና የጠበቀችው በቅዱስ ትውፊት ነውና። ስለዚህ ክርስቲያን፣ እንደ ጢሞቴዎስ "የተሰጠውን አደራ መጠበቅ" (1 ጢሞ. 6:20) አለበት። ይህም ማለት በቅዱሳት መጻሕፍት በምልዐት የተጻፈውንና በቤተ ክርስቲያን ትውፊት ከስህተት በጸዳ መንገድ የሚተረጎመውን አምላካዊ መገለጥ ማለት ነው።"[112]

በፊት ሉተራን ፕሮቴስታንት የነበረውና በኋላ ኦርቶዶክስ ክርስቲያን የሆነው ጃሮስላቭ ፔሊካን የተባለው ሊቅም እንዲህ ብሏል፦

የብሉይ ኪዳን መጻሕፍትን በትክክል ከመተርጎም እና የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍትን ቀኖና በትክክል ከመወሰን ጋር፣ ይህ የቤተ ክርስቲያን ትውፊት የቤተ ክርስቲያንን አስተምህሮ ለመወሰን . . . ወሳኝ የሆነ መለኪያ ነበር።

[111] Philip Schaff, Presbyterian/Reformed, *History of the Christian Church*, volume 3, page 606.
[112] JND Kelly, *Early Christian Doctrines*, page 47-48, 51.

> በ16ኛው መቶ ዓመት ከተፈጠሩ ውዝግቦች የተወለዱ አረዳዶችንና ቃላቶችን በ2ኛውና በ3ኛው መቶ ዓመት ውይይቶችና መረዳቶች ላይ ወስዶ መጫን በዚያ ዘመን ላይ ያልነበረ ነገርን የነበረ ለማስመሰል መሞከር ነው። ቅድመ ኒቂያ በነበረችው ቤተ ክርስቲያን 'መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ' የሚል እሳቤ አልነበረም፣ እንደዚሁም 'ትውፊት ብቻ' የሚል አስተምህሮም አልነበረም። ይህ ሐዋርያዊ ትውፊት ሕያው የነበረና በጎላና በተረዳ ሁኔታ ሊታወቅ የሚችል የነበረ በመሆኑ ሐዋርያት ለአስተምህሯቸው ቋሚ ማስረጃ ይሆን ዘንድ ቅዱሳት መጻሕፍትን ባይጽፉ እንኳ ኖሮ፣ ቤተ ክርስቲያን ሐዋርያት ቤተ ክርስቲያንን ሲያስረክቡ ላስረከቧቸው አባቶች ባቀበሏቸው ትውፊት ለመመራት በምትችልበት ሁኔታ ላይ ነበረች።[113]

ስለሆነም ቤተ ክርስቲያንን ከፊደሉ አልፎ ወደ ቃሉ ሐሳብና ምስጢር አስተማማኝ በሆነ ሁኔታ ለመግባትና ለመረዳት የሚያስችላት ትውፊት ብቻ ነው። ስለዚህ "ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ሌላ ትውፊት የሚባል ነገር የለም" የሚለው የፕሮቴስታንቶች የመከራከሪያ ነጥብ መጽሐፍ ቅዱሳዊም፣ ታሪካዊም ማስረጃም ሆነ መሠረት የለውም።

## 1.15 መጽሐፍ ቅዱስ እና ትውፊት - በቤተ ክርስቲያን ቀደምት አበው ትምህርት

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን በቂ ነው፣ ማንም ሰው በተረዳበት መንገድ በግሉ ሊተረጉመው ይችላል" የሚለው አስተምህሮ ከዘመነ ሐዋርያት አንሥቶ በነበረችው የቤተ ክርስቲያን ትምህርት ሲመዘን ታላቅ ስህተት ነው፣ የስህተቶች ሁሉ ምንጭም ነው። ሆኖም አንዳንድ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ባይ ፕሮቴስታንቶች ይህ አስተምህሯቸው በእነ ሉተር የተጀመረ ሳይሆን ከጥንት ጀምሮ የነበሩት የቤተ ክርስቲያን አባቶች አስተምህሮና አቋም እንደሆነ አድርገው ለማሳየት መሞከራቸው አልቀረም።

ይህን ለማሳካት የሚሞክሩትም አንዳንድ አባቶች ስለ መጽሐፍ ቅዱስ እውነተኛነትና አስፈላጊነት የተናገሯቸውን ነገሮች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ያሉና ትውፊትን የማይቀበሉ የነበሩ አስመስሎ በማቅረብ ነው። ሆኖም እነዚህ አባቶች ስ መጽሐፍ ቅዱስ ጠቃሚነትና በቂነት የገለጿቸው ሐሳች ፕሮቴስታንቶች "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ከሚሉት ሐሳ በተቃራኒው መሆኑን ቀጥሎ ባለው በ1.152 እናገኛለን፣ ስለሆነም ከዚህ ቀጥሎ ከዘመነ ሐዋርያውያን አበው አንሥቶ የነበሩ የቤተ ክርስቲያን

[113] Jaroslav Pelikan, *The Christian Tradition: A History of the Development of Doctrine* volume 1, page 115-117.

የቀደምት አባቶች ስለ መጽሐፍ ቅዱስ እና ስለ ትውፊት የነበራቸውን አስተምህሮና እምነት እንመለከታለን።

## 1.15.1 መጽሐፍ ቅዱስን በተመለከተ የአባቶች ትምህርት

**ቅዱስ አትናቴዎስ ሐዋርያዊ**

- “. . . የእውነት ትምህርት የበለጠ አስተማማኝ የሚሆነው ከሌላ ምንጭ ይልቅ ከመጽሐፍ ቅዱስ ሲቀዳ ነው።" (በእንተ ጉባኤ ኒቂያ፣ 31)
- “እውነትን ለመስበክ የተቀደሱና እስትንፋሰ እግዚአብሔር የሆኑት ቅዱሳት መጻሕፍት በራሳቸው በቂዎች ናቸው።" (በእንተ አሕዛብ፣ 1:1)
- “በእነርሱ ውስጥ ካለው አምላካዊ ቃል ጠጥቶ ይረካ ዘንድ እነዚህ ቀኖናውያት መጻሕፍት የድኅነት ጅረቶች ናቸው፤ የእምነት ቤት [ቤተ ክርስቲያን] ወንጌልን የምትሰብከው በእነዚህ ብቻ ነው፤ ከእነርሱ ላይ ማንም ሰው ቢሆን አይውሰድ (አይቀንስ)፣ አይጨምርባቸውም።" (የፋሲካ መልእክት፣ መልእክት 39)

**ቅዱስ ቄርሎስ ዘኢየሩሳሌም**

- “እምነታውያትና የተቀደሱ የሆኑትን የእምነትን ምስጢራት በተመለከተ በጣም ትንሽ የሚባለው ነገር እንኳ ያለ ቅዱሳት መጻሕፍት ሊሰጥ አይገባውም። በክርክር ጥበብና አማላይ በሆኑ ቃላት እንዳትታለሉና ወደ ስህተት እንዳትገቡ ተጠንቀቁ። እነዚህን ነገሮች የምነግራችሁ እኔ ራሴ እንኳ ብሆን እየነገርኳችሁ ስላለሁት ነገር ማስረጃና ማረጋገጫ የሚሆን ነገር ከመጽሐፍ ቅዱስ ካላገኛችሁ በስተቀር እንዲሁ ዝም ብላችሁ አትመኑኝ። የምናምንበት የመዳን ነገር የሚረጋገጠው በሰዎች የአመክንዮ ብልሃትና ችሎታ ሳይሆን ከቅዱሳት መጻሕፍት ነው።" (ትምህርት 4:17)
- “ምናልባት እንዳትታለል ትኩረትህን የእኔ አነጋገርና የቋንቋ አጠቃቀም ችሎታ ላይ አታድርገው፤ በእያንዳንዱ ነጥብ ላይ የነቢያትን ምስክርነት ካላገኘህ በስተቀር የሚባለውን ሁሉ እንዲሁ ዝም ብለህ አትመን። ከቅዱሳት መጻሕፍት ከእርሷ ስለሚወለድባት ስለ ድንግል፣ ስለ ቦታው፣ ስለ ጊዜው፣ ስለ ሥጋዌው (ሰው ስለ መሆኑ) ሁኔታ ከመጽሐፍ ቅዱስ ካልተማርክ እንዲሁ ዝም ብለህ አትቀበል። የሰውን ምስክርነት አትቀበል (ዮሐ. 5:34)" (ትምህርት 12:5)

- "ስለዚህም መንፈስ ቅዱስ እርሱ ባወቀ ያስጻፈልንን እንጠቀምበት፤ ስላልተጻፈው ነገር ራሳችንን በማባዘን አንጥመደው። መንፈስ ቅዱስ ቅዱሳት መጻሕፍትን ጽፎልናል፤ እናውቀው ዘንድ የሚገባንን ሁሉንም ተናግሮናል፤ ስለዚህ እርሱ በነገረን ራሳችንን እንገድብ፤ ከዚያ ውጭ ማድረግ ጥንቃቄ የማጣት ግድ የለሽነት ነውና።" (ትምህርት 16፡2)

## ቅዱስ ዮሐንስ አፈ ወርቅ

- "ስለዚህ ወይም ስለዚያ ጉዳይ ያላችሁን ጥያቄ ታቆሙና እነዚህን ነገሮች በተመለከተ ያሏችሁን ጥያቄዎች ሁሉ ወደ ቅዱሳት መጻሕፍት ትመሯቸው ዘንድ እለምናችኋለሁ።" (ትርጓሜ መልእክተ ቆሮንቶስ ካልእ፣ ክፍለ ትምህርት 13)
- "ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ የሆነ ነገር ከተነገረ የሰሚዎቹ ማሰብ ሽባ ይሆናል። ሆኖም ምስክሩ አምላካውያት ስጦታ ከሆኑት ከቅዱሳት መጻሕፍት የተገኘ ሲሆን ግን የሰባኪውን ትምህርትም የሰሚውን ነፍስም ሁለቱንም ያጸናቸዋል፤ ያጠነክራቸዋል።" (ትርጓሜ ዳዊት፣ መዝሙር 59)
- "እንደ አስተማማኝ መዝጊያ፣ ቅዱስ መጽሐፍ መናፍቃንን ይዘጋባቸዋል፤ እኛንም ከስህተት ይጠብቀናል።" (ትርጓሜ ወንጌለ ዮሐንስ፣ ክፍለ ትምህርት 58)

## ቅዱስ ሄሬኔዎስ

- "ሐዋርያት በዚያ ጊዜ መጀመሪያ ወንጌልን ሰበኩ፤ ኋላ ግን በእግዚአብሔር ፈቃድ የእምነታችን መሠረትና ዓምድ ይሆነን ዘንድ በቅዱሳት መጻሕፍት ውስጥ ጽፈው ለእኛ ሰጡን፤ ።" (በእንተ መናፍቃን፣ 3፡1፡1)
- "ከሐዋርያት የሆነው ትውፊት በቤተ ክርስቲያን ያለ ስለሆነና በእኛም ዘንድ የጸና ቀዋሚ ስለሆነ፤ ወንጌልን በጻፉልን በእነዚያ ሐዋርያት ወደሚሰጡን መጽሐፋዊ ማረጋገጫ እንሂድ፤ . . ." (በእንተ መናፍቃን፣ 3፡5፡1)

## ቅዱስ ባስልዮስ ዘቂሳርያ

- "በቅዱሳት መጻሕፍት ትምህርት የተማሩ ሰማዕያን በሰባኪዎቹ የሚነገረውን ነገር መመርመርና መፈተሽ፤ ከዚያም ከቅዱሳት መጻሕፍት ጋር የሚስማማውን መቀበል፤ ለእነርሱ [ለቅዱሳት መጻሕፍት] ባእድ የሆነውን ደግሞ ውድቅ አድርገው መጣል ይገባቸዋል።" (ቅዱስ ባስልዮስ፣ Moralia 72,1)
- "የእግዚአብሔር መንፈስ የቃኛቸው ቅዱሳት መጻሕፍት በመካከላችን ዳኛ ይሁኑ፤ ከእግዚአብሔር ቃል ጋር የሚስማማ አስተምህሮ ለያዘው ወገን

ለእርሱ የእውነት ድምፅ ይሰጥለታል።" (ቅዱስ ባስልዮስ፡ መልእክት ኀበ ኤዎስጣቴዎስ)

## ሌሎች አባቶች

- "መጽሐፍ ቅዱስ ምስክር የማይሰጥለትን ማንኛውንም ነገር እውነት ነው ብለን ልንመሰክርለትና ልናረጋግጥ እንዴት እንችላለን?" (ቅዱስ ቄርሎስ ዘእስክንድርያ፡ ትርጓሜ ዘፍጥረት)
- "ቅዱስ መጽሐፍ በዝምታ ያለፋቸው ነገሮች፡ ከዚያ አልፎ ሊመረመሩ የማይገባቸው መሆኑ ግልጽ ነው። መንፈስ ቅዱስ ለጥቅማችን የሚሆነውን ነገር ሁሉ ሰጥቶናልና።" (አናስታስዮስ ዘአንጾኪያ)
- "ቅዱሳት መጻሕፍትን አለማወቅ ክርስቶስን አለማወቅ ነው።" (ጄሮም፡ ትንቢተ ኢሳይያስ መቅድም)
- "የሰዎችን አእምሮና ሐሳብ መከተልና ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጭ ሌላ አምላካዊ የሆነ ነገር አለ ማለት ክርኩሳን መናፍስት የሚመነጭ ሰይጣናዊ ግብር ነው።" (ቅዱስ ቴዎፍሎስ ዘአንጾኪያ)

ስለሆነም የቤተ ክርስቲያን አባቶች በመጽሐፍ ቅዱስ አምላካዊ መጽሐፍነትና ሥልጣን የሚያምኑ ሲሆኑ፡ (አንዳንዶቹም ሁሉም የክርስትና አስተምህሮዎች በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ቢያንስ በምልክታ ደረጃም እንኳ ቢሆን አሉ ያሉ ሲሆን)፤ ማናቸውም ግን "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" በሚለው፤ ማለትም መጽሐፍ ቅዱስ ከቤተ ክርስቲያን ትውፊትና ሕያው ከሆነው የክርስትና እምነት ውጭ ለብቻው ተነጥሎ በቂ ነው ብለው አምነውም አስተምረውም አያውቁም። ስለዚህ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው አስተምህሮ የጥንቷ ቤተ ክርስቲያንና የቤተ ክርስቲያን አባቶች ሁሉ አስተምህሮ ነበር" የሚለው ምኞትን እውነት የማስመሰል ስልት ከመሆን ያለፈ አንዳችም እውነትነት የለውም።

ይህን አባባል የቤተ ክርስቲያን ታሪክን ደኅና አድርገው የሚያውቁ ፕሮቴስታንቶች ራሳቸው አይቀበሉትም፡ ስህተትነቱንም ደጋግመው ገልጸዋል። "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን በቂ ስለሆነ የቤተ ክርስቲያን ትውፊትና መርሐ እምነት አያስፈልግም" ብሎ የጻፈ አንድ የቤተ ክርስቲያን አባት ትምህርት እንኳ ማቅረብ አይችሉም። ከቅዱስ ሄሬኔዎስ፡ ከቅዱስ አትናቴዎስ፡ ከቅዱስ ቄርሎስ ዘኢየሩሳሌም፡ ከቅዱስ ባስልዮስ፡ ከቅዱስ ጎርጎርዮስ ነባቤ መለኮት፡ ከቅዱስ ዮሐንስ አፈወርቅ፡ ከቅዱስ ቄርሎስ ዘእስክንድርያና ከመሳሰሉት "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" ብሎ ያመነና ያስተማረ ማንም የለም። ይህን ከዚህ ቀጥሎ ከራሳቸው ከአባቶቻችን ትምህርት እንስማ።

## 1.15.2 ትውፊትን በተመለከተ የአባቶች ትምህርት

### ቅዱስ አትናቴዎስ ሐዋርያዊ

- "የኦርቶዶክሳዊት ቤተ ክርስቲያን ትውፊቷ፣ አስተምህሮዋ፣ እና እምነቷ ከመጀመሪያ በሐዋርያት የተሰበከና በአባቶች የተጠበቀ ነው። ቤተ ክርስቲያን የተመሠረተችው በዚህ ነው፤ ከዚህ የሚያፈነግጥ ማንም ቢኖር አሁንም ክርስቲያን አይደለም፣ ለወደፊትም ክርስቲያን ተብሎ ሊጠራ አይገባውም።" (መልእክት ኀበ ሴራጲዮን)

- "እኛ ክርስቲያኖች የያዝነውን እምነት ጭብጥ ሐሳቡን ልብ ብለን ከተረዳን፣ ሐዋርያው እንደሚያስተምረን ይህን የእምነት ጭብጥ አረዳድ እንደ መርሕ (መመሪያ) በመጠቀም ቅዱስ መጽሐፍን ወደ ማንበብ በዚህ ሁኔታ እንግባ። የክርስቶስ ጠላቶች ይህን መሠረታዊ የክርስትና እምነት ጭብጥ የማያውቁ ከመሆናቸው የተነሣ ከእውነት መንገድ ወጥተው ጠፍተዋል፤ ማሰብ በማይገባቸው መንገድ በማሰብ በመሰናከያ ድንጋይ ላይ ወድቀው ተሰናክለዋል።" (ትምህርት በእንተ አርዮሳውያን፣ 3፡28)

- "እርሱን [ዲያብሎስን] በመከተልና ከእርሱ ጋር በመሆን መናፍቃን ሁሉ መጽሐፍ ቅዱስን ይጠቅሳሉ፤ ሆኖም ቅዱሳን አባቶች እንዳስተላለፉልንና እንዳስረከቡን ያለ እምነት ግን የላቸውም። እነዚህን የአባቶቻችንን ትውፊት እንደ ሰዎች ትውፊቶች በመቁጠርና ባለመቀበል ስህተት ላይ ወድቀዋል፣ ምክንያቱም እነዚህን በአግባቡ አያውቋቸውምና፣ ኃይላቸውንም አይገነዘቡምና ነው።" (የትንሣኤ መልእክት፣ 2)

- ". . . ይህ እምነትና አረዳድ ከአባት ወደ አባት ሲተላለፍ እንደኖረና ከእኛ እንደ ደረሰ በማስረጃ አረጋገጥን። የዘመናችን አይሁዶች [አርዮሳውያን] ሆይ፣ የቀያፋ ደቀ መዛሙርት ሆይ፣ እናንተ ለምትሏቸው ነገሮች ስንት አባቶችን መጥቀስ ትችሉ ይሆን? ጥበበኛና አስተዋዮች ከሆኑት መካከል አንድም እንኳ ልትጠቅሱ አትችሉም፤ ሁሉም የእናንተን ክህደት ይጸየፉሉ እንጂ! ከዲያብሎስ በስተቀር ሌላ ልትጠቀሱት የምትችሉት የቤተ ክርስቲያን አባት የላችሁም። በክህደት አባታችሁ ሌላ ማንም ሳይሆን እርሱ ብቻ ነው። . . ." (በእንተ ጉባኤ ኒቂያ፣ 27)

- "እውነተኛ ልጆች ከሆንንና ድቃላዎች ካልሆንን በስተቀር ለአባቶች በጎ ሕሊና ይኖረን ዘንድ የተገባና ትክክል የሆነ ነገርም ነው። ትውፊታችንን የተቀበልነው ከእነርሱ ነውና፣ የሃይማኖት ትምህርትን ያገኘነውም ከእጃቸው

ነውና።" (በእንተ ሲኖዶሳት ዘእርሚኒየም ወሴሌውቅያ፣ 47)

- "... በሐዋርያት መሠረት ላይ ቆመህ፣ የአባቶችን ትውፊት አጽንተህ ያዝ፣ በቤተ ክርስቲያን ላይ የተነሡ ሁከቶችና ሽኩቻዎች ሁሉ ያበቁ ዘንድና የመናፍቃን ክንቱ ጥያቄዎች ሁሉ ይወገዱ ዘንድ ጸልይ።" (በእንተ ሲኖዶሳት ዘእርሚኒየም ወሴሌውቅያ፣ 54)
- "አጠቃላይ የሆነውን የእምነት ዕይታ (Scope of Faith) በመያዝ እነርሱ [አርዮሳውያን] አበላሽተው በተሳሳተ መንገድ የሚተረጉሟቸው ጥቅሶች ትክክለኛ የሆነ ትርጓሜ ያላቸው መሆኑን እንረዳ።" (ትምህርት በእንተ አርዮሳውያን፣ 3:35)
- "... የክርስቶስ ጠላቶች [አርዮሳውያን] ቤተ ክርስቲያናዊ የሆነውን ዕይታና አረዳድ እንደ እምነታቸው መልሕቅ አድርገው ተቀብለው ቢሆን ኖሮ በእምነታቸው ስተው ባልጠፉና ባልሰጠሙ ነበር።" (ትምህርት በእንተ አርዮሳውያን፣ 3:58)
- "መናፍቃን እንደ ራሳቸው የግል ስሜትና አረዳድ የሆነ የተሳሳተ አተረጓጎምን በአምላካዊው ቃል ላይ ይጭኑበታል።" (ትምህርት በእንተ አርዮሳውያን፣ 1:37)

ቅዱስ ባስልዮስ ዘቂሣርያ

- "መንፈስ ቅዱስን በተመለከተ ከቅዱሳት መጻሕፍት እና ከአባቶቻችን ያልተጻፉ ትውፊቶች (*the Unwritten Tradition of the Fathers*") የተቀበልናቸውን እንመልከታቸው። ..." (በእንተ መንፈስ ቅዱስ፣ 22)[114]
- በቅድስት ቤተ ክርስቲያን የተቀበልናቸውና የሚጠበቁት አስተምህሮዎችና ተግባራዊ ድርጊቶች (ይትበሃሎች) የተወሰኑትን ከተጻፈው አስተምህሮ ያገኘናቸው ናቸው፤ ሌሎቹን ደግሞ በምስጢራቱ በኩል በሐዋርያት ትውፊት የተቀበልናቸው ናቸው። እውነተኛ አማኒነትን በተመለከተ እነዚህ ሁለቱም እኩል ሥልጣን አላቸው።"[115] (በእንተ መንፈስ ቅዱስ፣ 27)

---

[114] "Let us now investigate what are our common conceptions concerning the Spirit, as well those which have been gathered by us from Holy Scripture concerning It as those which we have received from the unwritten tradition of the Fathers.

[115] "Of the beliefs and practices whether generally accepted or enjoined which are preserved in the Church some we possess derived from written teaching; others we have delivered to us in a mystery ***by the Apostles by the TRADITION of the Apostles; and both of these in relation to true religion have the SAME FORCE***"

- "'ወምስለ ቅዱስ መንፈስ - ከመንፈስ ቅዱስ ጋር' የሚለው የጸሎት የምስጋና ቃል የተጻፈ ምንጭ የለውም ለሚለው ተቃውሞ በተመለከተ የምንለው ይህን ነው፡- የተጻፈ ካልሆነ በስተቀር የምናምነውም ሆነ የምንጸልየው ሌላ አንድም ነገር የሌለ ከሆነ፣ አዎ ይህንም ልንቀበለው አይገባም። ነገር ግን በቤተ ክርስቲያን ሕይወት የምንፈጽማቸውና የምናምናቸው ምስጢራቶቻችን ብዙዎቹ የተጻፈ ማስረጃ ስላላቸው ሳይሆን በትውፊት የተቀበልናቸው በመሆናቸው ከሆነ፣ ይህንንም ይህን ከመሰሉ ከሌሎች ብዙ ነገሮች ጋር እንዲሁ አብረን እንቀበለው። ባልተጻፉ ትውፊቶች መመራትና እነርሱን መጠበቅ ሐዋርያዊ ነው ብዬ አምናለሁና።[116] "ወንድሞች ሆይ፣ በሁሉ ስለምታስቡኝና አሳልፌ እንደ ሰጠኋችሁ ወግን ፈጽማችሁ ስለ ያዛችሁ አመሰግናችኋለሁ" (1 ቆሮ. 11፡2) ተብሏልና። እንደዚሁም "እንግዲያስ፣ ወንድሞች ሆይ፣ ጸንታችሁ ቁሙ፣ በቃላችንም ቢሆን ወይም በመልእክታችን የተማራችሁትን ወግ ያዙ" (2 ተሰ. 2፡15) ተብሏልና። . . . ከእነዚህ ትውፊቶች አንዱ አሁን ከፊታችን ያለውና ከመጀመሪያ ጀምሮ በሐዋርያዊነታቸው ያስተማሩት፣ በአብያተ ክርስቲያናቱ ሁሉ በጽኑ የተከሉት፣ ለተከታዮቻቸው ያስረከቡት፣ አገልግሎት ላይ የመዋሉ ነገርም በረጅም ዘመን ይትበሃልና ልማድ በየጊዜው ቀስ በቀስ እየጎለበተ የሄደ ነው። . . ." (በእንተ መንፈስ ቅዱስ፣ 71)

- "ከራሳቸው ግላዊ አረዳድና እምነት ይልቅ የአባቶች የትምህርት ድምፅ የበለጠ ሥልጣንና ኃይል ያለው መሆኑን አለመቀበል በትዕቢት የተመላ እንደመሆኑ ተግሣጽ ይገባዋል።" (መልእክት ኀበ ካኖኒካስ)

- "እኛን ይወጉበት ዘንድ [አርዮሳውያን] በእኛ ላይ ያዘጋጇቸውን የጦር ዕቃቸውን ሁሉ ዝግጁ አድርገው ሰልፈውብናል። . . . እኛን ማጥቃታቸው ለጦርነቱ ሰበብ መፈለጊያ ሽፋን ሲሆን የጥቃታቸው እውነተኛው ዒላማቸው ሃይማኖታችን ነው። የእውነተኛው ሃይማኖታዊ አስተምህሮ ጠላቶች የሆኑት የሁሉም ዓላማ ሐዋርያዊውን ትውፊት በማፍረስ የክርስቶስን ሃይማኖት ከመሠረቱ ማናወጽና ሙሉ በሙሉ ማጥፋት ነው። ስለዚህም ልክ ገንዘብ

[116] "In answer to the objection that the doxology in the form 'with the Spirit' *has NO written authority,* we maintain that *if there is not other instance of that which is UNWRITTEN, then this must not be received.* But if the *GREAT NUMBER of our mysteries are admitted into our constitution WITHOUT written* authority, then, in company with many others, let us receive this one. *FOR I HOLD IT APOSTOLIC TO ABIDE BY THE UNWRITTEN TRADITIONS.*

እንደ ተበደሩ ተበዳሪዎች የተጻፈ ማስረጃ ይቀርብላቸው ዘንድ ይጮኻሉ።[117] ያልተጻፉትን የአባቶቻችንን ትውፊቶች ሁሉ ጥቅም እንደ ሌላቸው ነገሮች እንቀበላቸውም ይላሉ። . . ." (በእንተ መንፈስ ቅዱስ፣ 25)

- "ለእኔ መጠመቄ የሕይወቴ መጀመሪያ ነበር፣ ዳግመኛ የተወለድኩባት ያች ቀንም የቀኖቼ መጀመሪያ ናት። ስለዚህም በጥምቀታችን ጊዜ የምንለው ነገር ከሁሉም በላይ እጅግ የከበረ ነገር ነው። ታዲያ በእነዚህ ሰዎች [በአርዮሳውያን] አማላይ ቃላቶች በመታለል፣ ቀድሞ በኃጢአት ምክንያት የእግዚአብሔር ጠላት የነበርኩ ሆኜ ሳለ የእግዚአብሔር ልጅ የተደረግኩበትን፣ እግዚአብሔርን የማወቅን ጮራ ወዳሳየኝ ብርሃን የመራኝን ትውፊት ልተው እችላለሁን?"[118] (በእንተ መንፈስ ቅዱስ፣ 26)

- ". . . ሕይወትን በሚሰጠው ጸጋ የተሰጠን ትውፊት ለዘለዓለም የጸና ሆኖ መጠበቅ አለበት።" (በእንተ መንፈስ ቅዱስ፣ 28)

- ". . . የመጠመቂያውን ውኃ (ማየ ጥምቀት) እና ቅብዐ ሜሮኑን እንባርካለን፣ ተጠማቂውንም እንዲሁ [እንባርከዋለን]። ይህ ትእዛዝ ተጽፎ የተገኘው ከየትኛው መጽሐፍ ላይ ነው? ይህ ከምስጢራተ ቤተ ክርስቲያን ጋር አብሮ የተቀበልነው ትውፊት አይደለምን? በቅብዐ ሜሮን መቀባትንስ ያስተማረን የትኛው የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ነው? ተጠማቂውን በመጠመቂያው ውኃ ውስጥ ሦስት ጊዜ እየገባና እየወጣ እንዲጠመቅ ማድረግስ ከየት ተገኘ? ከምስጢረ ጥምቀት አፈጻጸም ጋር ያሉ ሌሎች ተያያዥ ጉዳዮች፣ እንዲሁም ሰይጣንንና ሠራዊቱን መካድስ ከየትኛው ቅዱስ መጽሐፍ ተገኙ? እነዚህ የመጡትና ያገኘናቸው አባቶቻችን የምስጢራቱን ቅድስና በጸጥታ ይጠበቁ ዘንድ በሚገባ የተማሩ እንደመሆናቸው፣ ለአላስፈላጊ ድፍረትና ለሞኞች ምርምር ክፍት እንዳይሆኑ በምስጢር ይጠበቁ ዘንድ በዚያ ሁኔታ ከጠበቋቸው ካልተጻፉና ከምስጢራዊ አስተምህሮ አይደለምን? ኢጥሙቃን (ያልተጠመቁ) እንዲያዩዋቸው እንኳ የማይፈቀድላቸውን የእነዚህን ምስጢራት አስተምህሮ

---

[117] The one aim of the whole band of opponents and enemies of "sound doctrine" is to shake down the foundation of the faith of Christ by levelling apostolic tradition with the ground, and utterly destroying it. So like the debtors,—of course *bona fide* debtors—they clamour for written proof, and reject as worthless the unwritten tradition of the Fathers.

[118] For if to me my baptism was the beginning of life, and that day of regeneration the first of days, it is plain that the utterance uttered in the grace of adoption was the most honourable of all. Can I then, perverted by these men's seductive words, abandon the tradition which guided me to the light, which bestowed on me the boon of the knowledge of God, whereby I, so long a foe by reason of sin, was made a child of God?

በጽሑፍ ላይ ማስፈር እንዴት ትክክል ሊሆን ይችል ነበር?"119 (በእንተ መንፈስ ቅዱስ፣ 27)

❖ "በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ካሉትና ከሚጠበቁት አስተምህሮዎች አንዳንዶቹን ከተጻፈው አስተምህሮ ያገኘናቸው ሲሆኑ ሌሎቹን ደግሞ በሐዋርያት ትውፊት በምስጢራተ ቤተ ክርስቲያን አማካይነት የተቀበልናቸው ናቸው። እውነተኛውን ሃይማኖት በተመለከተ እነዚህ ሁለቱም እኩል ሥልጣን አላቸው። ይህንም የቤተ ክርስቲያንን ትምህርት ትንሽም እንኳ ቢሆን የቀመሰ ሰው አይቃወምም። እነዚህን ልማዶች የተጻፈ ምስክር ስለሌላቸው ብቻ አስፈላጊነታቸው ትንሽ ነው በሚል ውድቅ ልናደርጋቸው ብንሞክር ሳናውቀው ወንጌልን ከመሠረቱ እንጎዳዋለን፣ እምነታችንን የምንመሰክርባቸውን ነገሮች ሁሉ ተራ ቃላት ብቻ እንጂ ከዚያ ያለፈ ፋይዳ የሌላቸው እናደርጋቸዋለን።

"ለምሳሌም በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም የምናምነውን እኛን በመስቀል ምልክት እንድናማትብ በጽሑፍ ያስተማረን ማን ነው? በጸሎት ጊዜ ወደ ምሥራቅ እንድንዞር ያስተማረን ጽሑፍ የትኛው ነው? በምስጢረ ቁርባን ጊዜ በኅብስቱና በጽዋው ላይ የምንላቸውን ነገሮች በጽሑፍ ትቶልን ያለፈው ከቅዱሳን መካከል የትኛው ነው? የሐዋርያት መልእክቶች ወይም ወንጌል በመዘገበልን ብቻ የምናቆም ሳይሆን በመግቢያውና በማጠቃለያው ለአገልግሎቱ ጠቃሚ መሆኑን ስለምናምን ሌሎች ቃሎችን እንጨምራለን እንጂ፣ ይህንም ያገኘነው ካልተጻፈው ትምህርት ነው።

"በተጨማሪም የመጠመቂያውን ውኃ እና የሜሮኑን ዘይት እንባርካለን፤ ከዚህም ጋር የሚጠመቀውን ንዑሰ ክርስቲያንም እንባርከዋለን። ይህን የምናደርገው በምን ሥልጣን ነው? ምንጮቻችን ጸጥተኛው እና ምስጢራዊው ትውፊት አይደለምን?[120] ሦስት ጊዜ ብቅ ጥልቅ እያደረጉ የማጥመቅ ባህልስ ከየት ተገኘ? . . . ይህ አባቶቻችን አላስፈላጊ ምርመራ እንዳይደርስባቸው አድርገው በጸጥታ ከጠበቋቸውና ካስተላለፉልን ምስጢራዊ ትምህርት የመጣ አይደለምን? አምላካዊ የሆኑት የእነዚህ ምስጢራት የምስጢርነታቸው አስፈሪ ግርማ የበለጠ የሚጠበቀው በጸጥታ (ባለ መጻፍ) መሆኑን በሚገባ ያውቃሉና። ኢጥሙቃን የሆኑ ሰዎች በዓይናቸው እንኳ እንዲያዩዋቸው

[119] (Come they not from this unpublished and secret teaching, which our fathers guarded in a silence with which no prying curiosity might meddle, having been well taught to preserve the sanctity of the mysteries by silence? For how could it have been right to publish in writing the doctrine of these mysteries, which the unbaptized are not even allowed to look upon?").

[120] Is not our authority silent and mystical tradition?



[121] ("Dog
procla

የማይፈቀድላቸው የሆኑት እነዚህ ምስጢራት በተጻፈ ነገር ላይ በይፋ የሚጻፉና ለሁሉ ግልጥ የሚሆኑ አይደለምና።

"ታላቁ ነቢይ ሙሴ የደብተራ ኦሪቱን ሁሉንም ክፍል ለሁሉም ሰው ክፍት ያላደረገበት ምክንያት ምንድን ነበር? ለተቀደሱ ነገሮች ክብር የማይሰጡትን ከአጥሩ ውጭ እንዲቀሩ አደረጋቸው። የመጀመሪያውን ክፍል የተሻለ ንጽሕናና አክብሮት ላላቸው ሰዎች አደረገ፤ ሌዋውያንን ብቻ እግዚአብሔርን ለማገልገል የተገባቸው አደረጋቸው። መሥዋዕትንና የሚቃጠል መሥዋዕትን፣ እና ይህን የተመለከቱ ሌሎች ክህነታዊ ተግባሮችን ደግሞ ለካህናቱ አደረገ። ከካህናቱ መካከል የተመረጠ አንድ ብቻ ደግሞ ወደ ቅድስተ ቅዱሳኑ እንዲገባ አደረገ። ያውም ሁል ጊዜ ሳይሆን በዓመት አንድ ጊዜ ብቻ፣ ከዚያች እንዲት ቀንም ወደ ውስጥ ገብቶ ቅድስተ ቅዱሳኑን ይመለከትና በዚያ ያለውን እንግዳና ልዩ የሆነ ነገር አይቶ ያደንቅ ዘንድ ለሚገባበት የተመደበ ጊዜ (ሰዓት) ነበረው። ሙሴ ሁል ጊዜ በየዕለቱ የሚደጋገምንና የተለመደ የሆነን ነገር መቃለልና ንቀት እንደሚከተለው፣ በአንጻሩ ያልተለመደና እንግዳ የሆነን ነገር ደግሞ ጉጉትና አክብሮት የማይለየው መሆኑን ያወቀ ብልህ ነበር። ልክ እንደዚሁም ሁሉ ከመጀመሪያው ጀምሮ ለቤተ ክርስቲያን ሕግን የሠሩላት ቅዱሳን ሐዋርያትና አባቶቻችንም በተመሳሳይ ሁኔታ የምስጢራቱን አስገራሚና አስፈሪ ግርማና ክብር በምስጢርና በጸጥታ (በመጻፍ ያይደለ) ጠበቁት፤ ለሁሉም በይፋ ግልጥ የሆነ ነገር ምስጢር አይሆንምና።

"ያልተጻፉ አስተምህሮዎቻችንና ተግባራዊ ድርጊቶቻችን የመኖራቸው ምክንያቱ ይኸ ነው። እርሱም የአስተምህሮዎቻችን ("Dogma") እውቀት ከመላመድ የተነሣ በብዙኃኑ እንዳይቃለልና ችላ እንዳይባል ነው። ዶግማ ("Dogma") እና ኬሩግማ ("Kerugma") ሁለት ራሳቸውን የቻሉ ነገሮች ናቸው፤ ዶግማ ("Dogma") በጸጥታ የሚጠበቅና የሚከወን ነው፣ ኬሩግማ ("Kerugma") ደግሞ ለዓለሙ ሁሉ የሚሰበክና የሚገለጥ ነው።121 የዚህ ዝምታ አንዱ መገለጫ ገጽታ በመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅም ላይ የዋለው ሰወር ያለ አገላለጽ ሲሆን፣ ይህም የዶግማዎችን ትርጉም ለመረዳት አስቸጋሪ የሚያደርጋቸውና ለሰሚው የሚጠቅመው ነገር ነው። ስለዚህም በጸሎታችን ጊዜ ወደ ምሥራቅ እንመለከታለን፣ ሆኖም እንዲህ ስናደርግ እግዚአብሔር በዔደን ገነት በምሥራቅ የተከላትን የጥንት አገራችንን ገነትን እየሻትን መሆኑን ግን የምናውቀው በጣም ጥቂቶች ነን። በሰንበተ ክርስቲያንና በበዓለ

121 ("Dogma" and "Kerugma" are two distinct things; the former is observed in silence; the latter is proclaimed to all the world.

- "የተከበራችሁ ወንድሞች ሆይ፣ በእኛ ላይ በጣም ከባድ የሆነ ስደት መጥቶብናል። በጎቻቸው ይበታተኑ ዘንድ እረኞች እየተሳደዱ ነው። . . . አሳዳጆቻችንም "ክርስቲያኖች ነን" የሚሉ [አርዮሳውያን] ናቸው። በአሳዳጆቻችን ዘንድ እንደ ከባድ ወንጀል የሚቆጠርና ከባድ የሆነ ቅጣትን እንደሚያስከትል እርግጠኛ የሆነ አንድ ክስ ቢኖር፣ የአባቶችን ትውፊት በጥንቃቄ መያዝና መጠበቅ ነው። በዚህ ምክንያት ኦርቶዶክሳውያን ከየቤታቸው እየተጋዙ ሩቅ ወደ ሆኑ ቦታዎች እንዲሰደዱ ይደረጋሉ። . . ." (መልእክት 243፣ ለጣሊያንና ለፈረንሳይ ጳጳሳት፣ የአብያተ ክርስቲያናትን ስቃያትና መከራዎች በተመለከተ)
- ". . . ወንድሞች ሆይ፣ የቤተ ክርስቲያን ምስጢራት እነዚህ ናቸው፣ የአባቶቻችን ትውፊቶች እነዚህ ናቸው። እግዚአብሔርን ለሚፈራና የእርሱን ፍርድ ለሚጠበቅ ለማንኛውም ሰው ሁሉ፣ ከእነዚህ ልዩ በሆኑ ትምህርቶች እንዳይወሰድ እመክራለሁ።" (መልእክት 261)

**ቅዱስ ቄርሎስ ዘኢየሩሳሌም**

- "የቤተ ክርስቲያን ትውፊታዊ ትምህርት ይህ ነው። . . . የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት እና የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት የትኞቹ እንደሆኑ ከቤተ ክርስቲያን ተግተህ ተማር።" (ትምህርት 5:33)
- "ሃይማኖትን ስትማርና ስትመሰክር፣ በቤተ ክርስቲያን በኩል አሁን የተሰጠህን ብቻ ገንዘብ አድርግ፣ እርሱን ብቻ ጠብቅ። ይህም ከቅዱሳት መጻሕፍት ሁሉ የተገኘና የዳበረ ነው።" (ትምህርት 5፡12)
- "የክርስቶስን ሥጋ ከተቀበልክ በኋላ ወደ ጽዋውም ቅረብ፣ እጆችህን ዘርግተህ ሳይሆን ጎንበስ ብለህ ቅረብ፣ በአምልኮና በአክብሮት መንፈስ ሆነህ ቅረብና የክርስቶስን ደሙንም ተቀበልና ራስህን ቀድስ። . . . ከዚያም ጸሎቱን ጠብቅ፣ እንዲህ ላለ ገናና ለሆነው ታላቅ ምስጢር ላበቃህ ለእግዚአብሔር ምስጋና አቅርብ። **<u>እነዚህን</u> <u>ትውፊቶች</u> እንዳይበረዙ አድርገህ አጽንተህ <u>ጠብቃቸው</u>**፣ ራስህንም ከበደል ነጻ አድርግ። ከቅዱስ ቁርባን ራስህን አትለይ፣ በኃጢአት ርኩሰት ከእነዚህ ቅዱሳትና መንፈሳውያት ምስጢራት ራስህን አታርቀው።" (በእንተ ምስጢራት፣ 5:21-22)

**ቅዱስ ዮሐንስ አፈ ወርቅ**

- ". . . ሐዋርያት ሁሉንም ነገር በመልእክት ጽፈው የሰጡን ወይም ያስተላለፉልን አለመሆናቸው ግልጽ ነው፣ ነገር ግን ብዙ ነገሮችን ሳይጽፉ በቃል አስተላለፉልን እንጂ። እነዚህ ሁለቱም - ማለትም የተጻፉትም

ጊዜም ሆነ በሰላም ጊዜ ሁሉ የተነገረ ስለሆነ፣ አንዳንዶች እንዲህ ያለ ክንቱ ሙከራ የማድረጋቸው ነገር፣ ሌሎቹ ደግሞ ዝም ጸጥ የማለታቸው ነገር ከየት መጣ?"[124] (መልእክት 101)

❖ "እኔ ከእግዚአብሔር አምላካዊ ድምፅ የሰማኋቸውን፣ በቅዱሳን አባቶቼ የተማርኳቸውን፣ በማንኛውም ሁናቴ ውስጥ ራሴን ከጊዜው ሁኔታ አንጻር ሳልለውጥ ያለመለወጥ ያስተማርኳቸውንና መቼም መች ቢሆን እነርሱን ከማስተማር ወደ ኋላ የማልላቸውን እነዚህን ትምህርቶች በጎቹም የእኔን ድምፅ ይሰሙኛል። እነዚህም የተወለድኩባቸው፣ እስከ ሞት ድረስ የምታመናቸው ትምህርቶች ናቸው።" (ትምህርት 33:15)

## ቅዱስ ጎርጎርዮስ ዘኑሲስ

❖ ". . . የእኛን እምነት እውነተኛነት ለማስረዳት ከአባቶቻችን የተቀበልነው ትውፊት ያለን መሆኑ በቂያችን ነው። ይህ የተቀበልነው ትውፊትም ከሐዋርያት ወደ እኛ፣ ከእነርሱ ቀጥሎ በመጡ በቅዱሳን አባቶቻችን በኩል በቅብብሎሽ የመጣና የወረስነው የእምነት ውርስ ነው።"[125] (በእንተ ዩኖሚየስ፣ 3:4)

❖ "አስተምህሯቸውን ወደዚህ እንግዳ ፈጠራ የሚለውጡ እነርሱ [አርዮሳውያን] . . . የሚሉት ነገራቸው እንደ አቧራ የቀለሉና ያልጸኑ ከሆኑት ሰዎች ሳይሆን ክብደት ካላቸውና ጽኑዓን ከሆኑት ሰዎች ዘንድ የእነርሱን እንግዳ ትምህርት የሚደግፉቸው ማግኘት የግድ ይላቸዋል። ሆኖም እነርሱ የሚሉት እንግዳ የሆነው ትምህርታቸው ከቀደሙ አባቶች ዘንድ መሠረት እንዳለው ሳያሳዩና ማረጋገጫውን ሳያቀርቡ እንዲሁ ከራሳቸው አንቅተው የሚሉት ነገር እስከሆነ ድረስ፣ የሐዋርያትንና የወንጌላውያንን ትምህርት፣ እንደዚሁም ከእነዚህ ቀጥሎ በቤተ ክርስቲያን እንደ ብርሃን ያበሩ የቅዱሳን አባቶችን ትምህርት በዚህ ማስረጃና ማረጋገጫ በሌለው በግብዞች ትምህርት እለውጣለሁ ብሎ እስከ መነሣት የሚደርስ ምን ዓይነት ሞኝና ደፋር ሰው ይኖር ይሆን!" (በእንተ ዩኖሚየስ፣ 4:6)

---

124 "I desire to learn what is this fashion of innovation in things concerning the Church...But since ***our faith has been proclaimed, both in writing and WITHOUT writing***, here and in distant parts, in times of danger and of safety, how comes it that some make such attempts, and that others keep silence?" **Epis 101**.

125 *It suffices for the PROOF of our statement that we have a TRADITION coming down from the FATHERS, an inheritance as it were, by SUCCESSION from the Apostles through the SAINTS who came after them.*"

## ሌሎች አባቶች

- "ሁሉም ነገር ከመጽሐፍ ቅዱስ ሊገኝ አይችልምና የትውፊትን ድጋፍና ርዳታ ማግኘት አለብን። ቅዱሳን ሐዋርያት የተወሰኑ ነገሮችን በጽሑፍ፣ ሌሎችን ግን በትውፊት ያስረከቡን ለዚህ ነው። ቅዱስ ጳውሎስ "እሳልፌ እንደ ሰጠኋችሁ" እንዳለ። 1 ቆሮ. 11፡2፣ 23፣ 15፡1" (ቅዱስ ኤጲፋንዮስ፣ **Panarion 61,6)**

- "ቤተ ክርስቲያን እናቱ ያልሆነች ሰው እግዚአብሔር አባቱ አይሆነውም። የክርስትና ሃይማኖት የሚጠበቀው በእውነተኛዋ ቤተ ክርስቲያን ትውፊት ነው።" (ቅዱስ ቆጵርያኖስ፣ መልእክት 74:11፣ በእንተ ዋሕድናሃ ለቤተ ክርስቲያን፣ 6)

- "የመጽሐፍ ቅዱስ ጥቅስ ማስረጃ አለን እያሉ የሚናገሩ ሰዎች አያታልሉህ፣ ራሱ ዲያብሎስም እንኳ ከመጽሐፍ ቅዱስ ጠቅሷልና። . . . እኛ ሁላችንም ብንሆን የመጽሐፍ ቅዱስን ቃል ጠቅሰን በገጸ ንባቡ ላይ እንግዳ የሆነ አዲስ አስተምህሮ ልንጭንበትና መጽሐፍ ቅዱስ እንደዚያ የሚል አስመስለን ልንናገርበት እንችላለንና።" (ቅዱስ ጀሮም፣ ተዋሥኦ በእንተ ሉሲፌራውያን)

### ማጠቃለያ

እነዚህ የቤተ ክርስቲያን አባቶች በአንድ በኩል መጽሐፍ ቅዱስ መሠረታዊ የቤተ ክርስቲያን የትምህርቷ መጽሐፍ መሆኑን፣ በሌላ በኩል ደግሞ መጽሐፍ ቅዱስን ማንም ሰው በራሱ መንገድ ሊረዳውና ሊተረጉመው የሚገባ ሳይሆን በቤተ ክርስቲያን የእምነት መርሕ ሊመራ የሚገባ መሆኑን እና ሁሉም ነገር በመጽሐፍ ቅዱስ ላይ የተጻፈ አለመሆኑን፣ ይህ ካልተጻፈ ትምህርት የመጣልን ትውፊትም እንደ ተጻፈው ሁሉ እኩል ጠቃሚና አስፈላጊ መሆኑን ሁሉም በአንድ ድምፅ ተስማምተው ጽፈውልናል። ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ መጽሐፍ ቅዱሳዊም ሆነ የቤተ ክርስቲያን አባቶች መሠረት የሌለው መሆኑ፣ ለማንም እውነትን በቅንነት ለሚፈልግ ሁሉ እንደ ንጋት ወጋገን ብሩህና ግልጽ ነው።

ክርስቶስ በትክክል ማን እንደሆነ ወይም እርሱን የምናመልከው እንዴት እንደሆነ ተጨባጭነት ያለው እና ታሪካዊ ማረጋገጫ ያለው እውቀትና መረዳት ልናገኝ የምንችለው ከሐዋርያት ጀምሮ ሳይቋረጥ በመጣው በቤተ ክርስቲያን ምስክርነትና በቅዱሳት መጻሕፍቶቿ አማካይነት መሆኑን የቤተ ክርስቲያን አባቶች አስተምረዋል።

የሐዲስ ኪዳን የመጻሕፍት ቀኖና ሂደት ከማለቁ በፊት የጻፈው ቅዱስ ሄሬኔዎስ፣ ቤተ ክርስቲያን የምታስተምረው ምን እንደሆነና እምነቱ የተመሠረተው ምን ላይ እንደሆነ በእርግጠኛነት ያውቅ ነበር። ይህ አባት እንደዚህ ያለውን ጽፎአል፦

> . . . እንደዚህ ያሉ ማረጋገጫዎችና ማስረጃዎች ያሉን በመሆኑ፣ ከቤተ ክርስቲያን በቀላሉ በግልጽ የሚገኘውን እውነት ከሌሎች ዘንድ መፈለግ አስፈላጊ አይደለም። . . . በሆነ ጉዳይ ላይ አለመግባባት ወይም ጥያቄ ቢፈጠር፣ ይህን ጉዳይ በተመለከተ ሐዋርያትን ያውቁ የነበሩትን በጣም ቀደምት የሆኑትን አብያተ ክርስቲያን ልንጠይቃቸውና ያንን ጉዳይ በተመለከተ ግልጽና እርግጠኛ የሆነውን ትምህርት ከእነርሱ ልንረዳ አይገባንምን? <u>ሐዋርያት መጽሐፍ ጽፈው ያልተውልን ቢሆን ኖሮስ?</u> <u>እነዚህ ሐዋርያት ይህን ትምህርትና እውነት አደራ የሰጧቸውን አብያተ ክርስቲያን የተቀበሉትን ትውፊት ልንቀበልና ልንከተል አይገባንምን</u>? (ቅዱስ ሄሬኔዎስ፣ ጸረ መናፍቃን፣ መጽሐፍ 3:4:1)

የሐዋርያትና የሐዲስ ኪዳን የመጻሕፍት ቀኖና ከማለቁ ብዙ ዘመናት ቀደም ብሎ፣ ሐዋርያቱም አንዳንዶቹ የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት ገና ከመጻፋቸው በፊት፣ በሐዋርያዊው ቅብብሎሽ አማካይነት፣ የቤተ ክርስቲያን እምነትና ምስጢራት እስከነ ሥርዓታቸው ድረስ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ይታወቁና ይተገበሩ ነበር። ስለዚህም ቤተ ክርስቲያን በተግባር እያኖረችውና እየተገበረችው የነበረውን ትምህርትና እውነት በተቻለ መጠን ለመግለጥ ይረዱ ዘንድ በኋላ የተጻፉትን የሐዲስ ኪዳን መጻሕፍት መንፈሳዊ ሐሳብ መረዳት የሚቻለው በቤተ ክርስቲያን ውስጥ በመሆን ብቻ ነው። ከዚያ ውጭ ሆኖ ጥቅሶችን እየነጠሉ በመጥቀስና ሐሳቡ እንዲህ ነው እንዲያ ነው እያሉ የግል አመለካከትን መሠረት እያደረጉ በመነታረክ የቅዱሳት መጻሕፍትን ሐሳብና እውነት ማግኘት አይቻልም! ፈጽሞ አይቻልም!

ቅዱሳት መጻሕፍትን በትክክል መረዳት የሚቻለው ከተገኙባትና የእርሷ የሆኑትን መጻሕፍት በቀኖና ከመለየት ተነሥቶ ስምና ቅደም ተከተል እስከ መስጠት ድረስ የወሰነቻቸው በቤተ ክርስቲያን መንፈስና ሕያው የሆነ ምሪት ብቻ ነው። መጽሐፍ ቅዱስ ብቻውን እንዳለ ሐሳቡን ለማወቅ በቂ ነው ካልን የዚህ ውጤት የሚሆነው መጻሕፍትን ለግላዊ አረዳድና አተረጓጎም ማጋለጥና እያንዳንዱ በራሱ ስሜትና መረዳት ወደደለሉ እንዲጎትታቸው ማድረግ ብቻ ነው። መጻሕፍቱን በተጻፉበት ዓላማና ሐሳብ እንድንረዳቸውና እንድንጠቀምባቸው የሚያደርገው ባለቤቶቻቸው የቤተ ክርስቲያን ትውፊት በነረዳቸው ብቻ ነው።

ማንኛውም ፕሮቴስታንት የቅድስት ሥላሴን አስተምህሮ ሲቀበል፣ የኢሉድን ሰንበተ ክርስቲያንነት ሲቀበል፣ መጽሐፍ ቅዱስን "የእግዚአብሔር ቃል" ነው ብሎ ሲያምን፣ "ኢየሱስ ክርስቶስ ፍጹም አምላክ ፍጹም ሰው ነው" የሚለውን አስተምህሮ ሲቀበል፣ በሐዲስ ኪዳን ያሉትን ከብዙ መጻሕፍት መካከል ቤተ ክርስቲያን መርጣ በቀኖና የወሰነቻቸውን መጻሕፍት ብቻ ሲቀበልና ሌሎቹን ሳይቀበል ሲቀር፣ በዚህ ሁሉ በመጽሐፍ ቅዱስ በጥቁርና በነጭ እንደዚህ ተብሎ ባይጻፍም እነዚህን በመቀበሉ የቤተ ክርስቲያንን ሕይወታዊ ትውፊት መቀበሉ ነው።

"መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የፕሮቴስታንቶች አስተምህሮ፣ "ማንም ሰው በመጽሐፍ ቅዱስ ስም ያሻውን እንዲል መንገዱን ወለል አድርጎ የከፈተ ነው። አናባፕቲስቶች አዲስና እኩልነት የሰፈነበት የተሻሻለ ክርስትናን እናሰፍናለን በማለት ነውጠኞች የሆኑት በመጽሐፍ ቅዱስ ስም "የተለያዩ የአበዳሪና ተበዳሪ ውሎችንና የንብረት ባለቤትነት መዝገቦችን አቃጥሉ የሚሉ መልእክቶችን በቀጥታ ከእግዚአብሔር ተቀብለናል" በሚል ነበር።

ኩዌከሮች ጥምቀትንና ምስጢረ ቁርባንን አያስፈልጉም ብለው እርግፍ አድርገው እንዲተው "ያሳመናቸው" መጽሐፍ ቅዱስ ነው። ጋብቻን በቤተ ክርስቲያን ማድረግን ንቅፈውና ትተው በዚያ ፋንታ "ደስ እንዳለህና እንደ ወደድህ በራስህ አድርገው" በማለት ከምስጢራዊነቱ ያፋቱት መጽሐፍ ቅዱስ እንዲህ ይላል በሚል ነበር። በየአገራቱ ያሉ "ነቢያት ነን" እያሉ ሕዝቡን የሚያታልሉና ብዙ ገንዘብ እንዲሰጧቸው የሚያደርጉትም ሕዝቡን ግራ የሚያጋቡባቸውና የሚያታልሉባቸው ጥቅሶችን በመጠቀም ነው።

ዳቪድ ኮሬሽ የተባለው ግለሰብ በአሜሪካ ቴክሳስ ውስጥ አፕሪል 19 ቀን 1993 (እ.ኢ.አ.) ተከታዮቹ ራሳቸውን አቃጥለው እስኪሞቱ ድረስ እንዲያምኑትና እንዲታዘዙት ለማሳመን የተጠቀመባቸውን ማሳመኛዎች ያገኘው ከመጽሐፍ ቅዱስ ነበር። ሞርሞኒዝምም አሳዋቂ የሆኑ ክርስቲያኖችን ክርስትናቸውን ትተው የእነርሱን እንግዳ የሆነ አምልኮና እምነት እንዲቀላቀሉ የሚጠቀሙበት ዋናው መሣሪያቸው መጽሐፍ ቅዱስ ነው።[126] ሊበራልና ሴኩላር፣ ግብረ ሰዶማውያንና ሌዝቢያን የሆኑ የተለያዩ የፕሮቴስታንት ቡድኖችም እነርሱ የሚያራምዷቸውንና የሚሏቸውን ሐሳቦቻቸውን ለማስረዳትና ለመደገፍ የሚጠቀሙት መጽሐፍ ቅዱስን ለራሳቸው በሚመቻቸው መንገድ በመጥቀስ ነው።

[126] Dancing Alone, p.194-95.

መጽሐፍ ቅዱስን የራሱ የሆነ አተረጓጎምና የትርጓሜ ታሪክ እንዳለው መጽሐፍ አድርጎ ሳይሆን ግላዊና ተአምራዊ የሆኑ መልእክቶችን ብቻ የሚናገር አድርጎ ማሰብ እና መጽሐፍ ቅዱስ ማለት ለእኔ የመሰለኝና እኔ የተረዳሁት ነው ብሎ ማንበብ፣ የክርስትና መንፈስ ሳይሆን የጥንቆላና የሙተት መጻሕፍት አነባበብ መንፈስ ነው። እንዲሁም ይህ ሁኔታ፣ "የክርስትና ሃይማኖት ኢምክንያታዊ የሆነ፣ አእምሯቸውና ስሜታቸው ያልተረጋጋ፣ ሞኛ ሞኝ የሆኑና በቀላሉ ተታላይ የሆኑ ሰዎች ሃይማኖት ነው" ለሚሉት ፌዘኛ ሴኪዩላሪስቶች አሳዛኝ የሆነ ማስረጃ አቀባይ የሆነ ነገር ነው።[128]

በቤተ ክርስቲያን ትውፊታዊ አረዳድ ፋንታ ሉተር "በተረዳኸው መሠረት ተርጉመው"፣ ካልቪን ደግሞ "የውስጥ ስሜትህን ተከተል" ብለው የጀመሩት ፀመጽ ክርስትና እንደ ክርስትና ሊጠራ ከማይችልበትና ሐዋርያዊ ከሆነው ክርስትና እጅግ የራቀና የተቃረነ የሆነ የፕሮቴስታንት እብደት ላይ አድርሶታል። የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናትን ሕይወት ከሆኑት ምስጢራትና በትክክለኛው ዐውድ ከሚጠብቁት ከሥርዐተ አምልኮና ከትውፊት ነጥለው ሕይወት አልባ በድን አድርገውታል።

ከዚህም በላይ አንደኛው ቢሳሳት ሊያርመው የሚችል ማንም ሌላ ስለሌለ በየጊዜው ስህተቶችን መፍጠር የሚያስችል የስህተት መፈልፈያ ጓዳ አድርገውታል። በታሪካዊቷ ቤተ ክርስቲያን አንድ ጳጳስ ወይም ካህን በሆነ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል ላይ የተሳሳተ ትምህርት ወይም አተረጓጎም ቢያስተምር በመላዋ ቤተ ክርስቲያን ይስተካከል ነበር። አልስተካከልም ካለም "ይህ የቤተ ክርስቲያን አስተምህሮ አይደለም" ተብሎ ይለይ (ይወገዝ) ነበር። በፕሮቴስታንቲዝም ግን ሁሉም ለየራሱ "ጳጳስ"፣ እና "ሲኖዶስ" ስለሆነ ስህተቱን እንደያዘ ሌሎችንም እንዳሳሰተ ይቀጥላል። ስለዚህም የፕሮቴስታንት የመጽሐፍ ቅዱስ ጥናት በመጽሐፍ ቅዱስ ስም ሐሰትና ክህደት የሚነገርበት፣ ለዚህ ሂደትም አንዳች ማቆሚያ የሌለው ሆኗል። የዚህ ሁሉ ምንጭ የሆነው ደግሞ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው የሐሰት አስተምህሮ ነው። ከላይ የጠቀስነው ፍራንክ ሻፈር በፕሮቴስታንቲዝም የነበረበትን ሕይወት በተመለከተ እንዲህ ብሏል፡-

> ውስጣችንን ለመልካም ምግባር ሕይወት ሊያነሳሳን፣ የቅድስናን ሕይወት በተግባራዊ መልኩ ሊያሳየን እና ምሳሌ ልናደርገው የምንችለው የቅዱሳን ሕይወት በእኛ ዘንድ የለንም። ከታሪካዊቷ ቤተ ክርስቲያን የጥበብ ምሕረት ማዕድ ከመብላት ጋ ራሳችንን በራሳችን ያራቅንና የከለከልን ነን። ከሁለት ሺህ ዓመት የተጠራቀመ ኖላዊ የጥበቃ ክምችት ጥበብና ልምድ የተራቆትን

[128] Dancing Alone, p. 197

ነበርን። ራሳችንን ብቻ ለራሳችን መሪዎች በማድረጋችንና ከዚያም ባለፈ ሥነ ልቡናዊ ዘዴዎች እኛ ላይ ከሚሞክሩብን በስተቀር ከዘመነ ሐዋርያት ጀምሮ ክርስቲያኖች ሲጠቀሙበትና ሲኖሩበት የነበረው ተግባራዊ ክርስትና እና ምስጢረ ንስሐ እኛ አልነበረንም። ይመራን ዘንድ መጽሐፍ ቅዱስ አለን፣ ሆኖም አብዛኛው ጊዜያችን ይጠፋና ያልፍ የነበረው የሆነ ጥቅስ ምን ማለት እንደሆነ በመከራከር ነበር። ባሕታዊው ቅዱስ ማርቆስ "ሙሉ በሙሉ በራስ ውሳኔና አካሄድ ላይ ብቻ በመተማመን ራስን ከሌሎች መለየትና ያለ ምንም ምስክር መቅረት በጣም አደገኛ ነው" ብሎ የጻፈው በራሳችን ድህ አደግ ስለ ሆንነው ስለ እኛ ስለ ፕሮቴስታንቶች የተናገረው ሳይሆን አይቀርም።[129]

"ተሐድሶ" ብለው የጠሩት የእነ ሉተር በ16ኛው መቶ ክፍለ ዘመን እንቅስቃሴ ከመጣ ጊዜ አንሥቶ የተፈጠረው ምን እንደሆነ ታሪክ በየዕለቱ በተግባር ይነግረናል። በአውሮፓ፣ በተለይ በጀርመን፣ አገር የእነ ሉተርን ተሐድሶ ተከትሎ ወዲያውኑ የመጣው ነገር፣ የተሐድሶ አስተምህሮ ቀጥተኛ ውጤት መንፈሳዊና ማኅበራዊ ቀውስና ምስቅልቅል ነበር።[130] ራሱ ሉተር እንኳ እርሱ የጀመረው ተሐድሶ ባስከተለው ውጤት በእጅግ ተጸጽቷል፤ እንዲህም ብሎ ነበር፡-

> እንዳለመታደል ሆኖ ዛሬ ሕዝቡ በወንጌል ውስጥ ሆነው ከባድና መራራ የሆነ ጥላቻንና መቀናናትን በማስተናድ ላይ ይገኛሉ። አስቀድሞ በፖፑ ሥር ከነበሩበት ጊዜ እጅግ በባሰ ሁኔታ በአስፈሪ ስግብግብነትና በገንዘብ ቀማኛነት ሥር ወድቀው ማየት የዕለት ተዕለት ተግባራችን ሆኗል።[131]

ሉተር ራሱ የጫረው እሳት ያደረሰውን አደጋ እንዲህ ባለ ሁኔታ በምሬትና በሐዘን ገልጿል። ግን ምን ዋጋ አለው?

የአገራችን ሉተራውያን ተሐድሶዎችም ልክ ሉተር እንደ ተጸጸተው ባለ ሁኔታ እንዲህ ብለዋል፡-

- "የተሐድሶ አስፈላጊነት ለፕሮቴስታንቶች" በሚል ርእስ ሥር እንዲህ ይላል፡- "ቤተ ክርስቲያን እንደየኃላፊነቱ የተወሰነ የግል ድርጅት በፈላጭ

[129] Dancing Alone, p. 229

[130] Msgr. Patrick F. O'Hare, LL.D., *The Facts about Martin Luther*, pp. 215-255.

[131] Walch, XIII, 2195, as quoted in The Facts About Luther, pp. 215-255.

> ቆራጭ መንፈስ ሆነው "ባለ ራእይ ነኝ" እያሉ በሌለ እውቀታቸው፣ የሌሎችን ግብአትና እገዛ በመናቅ ሞትን የሚያፋጥኑ መሪ ተብዬዎችን ቤቱ ይቁጠራቸው። . . . የእግዚአብሔር ቃል የበላይነትን በሰዎች ሕልም፣ ትንቢት፣ ኢመጽሐፍ ቅዱሳዊና ግላዊ አመለካከትና ልምምድ መተካት፤ . . በትንቢት፣ በራእይ፣ በሕልምና በእግዚአብሔር ይነግረኛል! ስም የመጽሐፍ ቅዱስ እውነትን እንደ አሳሪና ዘመን እንዳለፈበት ፋሽን የሚቆጥሩ የጠፉ አገልጋዮች ሕዝብን መረን እንዲሆን በማድረግ ላይ ይገኛሉ። አንዳንድ "የተቀቡ" አገልጋዮች ከእግዚአብሔር ቃል የተሻለ መገለጥ እንዳላቸው ራሳቸውን ለማስወደድ *"የመጽሐፍ ቃል ይነገር ወይስ ከሰማይ እንደ ወረደ ልናገር"*፣ *"እኔ ከላይ እንደ ወረደ እንጂ የመጽሐፍ ቅዱስ ምዕራፍና ቁጥር እየጠቀስኩ መናገር ካቆምኩ ቆይቻለሁ"* በማለትና *"በቃል የሚያገለግል"*፣ *"በጸጋ የሚያገለግል"* እያሉ ትልቅ ብኽርታን ፈጥረዋል። . . . (ገጽ 294-95)

የ "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" አስተምህሮ መጨረሻ ውጤቱ እንደዚህ ያለ ነው። አስተምህሮውን የሚከተሉት ሰዎች ራሳቸው በሚያስከትለው ውጤት ይመረራሉ፣ ግን የችግሩን ምንጭ እስካልተረዱትና ከእርሱ ነጻ እስካልወጡ ድረስ ችግሩ መቀጠሉ ግን አይቀርም። ስለሆነም "መጽሐፍ ቅዱስ ብቻ" የሚለው ሉተር የፈጠረው አስተምህሮ መጽሐፍ ቅዱሳዊ ያልሆነ፣ ሰው ሠራሽ ትምህርት መሆኑን በብዙ መንገድ አይተናል። ጌታችን "የሰው ሥርዓት የሆነ ትምህርት እያስተማሩ በከንቱ ያመልኩኛል" ያለው ቃል እንዳይደርስበት የሚፈልግ ሁሉ፣ ከዚህ ሉተር ሠራሽ ከሆነውና ራሱ የፈጠረው ሉተር እንኳ ከተጸጸተበት ትምህርት ሊርቅ ይገባዋል። ማቴ. 15፡9